ማውጫ

## የአዘጋጁ ማስታወሻ

በርካቶች የምንኖርበት ዓለም ቀውስ የበዛበት ነው ይላሉ፡፡ ከቅርብ ጊዜያት ወዲህ በዓለማችን ውስጥ ሁነቶች እየተከሰቱ የሚያልፉበት የጊዜ ፍጥነት ነዋሪዎቿን ረፍት ነስቷቸዋል፡፡ በዚህ ላይ ለነገሮች ትርጉም ለመስጠት የሚደረገው ፍጭት በመዓበል ውስጥ በምትናጥ ታንኳ ላይ እንደተሳፈሩ አድርጓቸዋል፡፡

የአገራችን ኢትዮጲያ የቅርብና እና አሁናዊ ሁኔታም ከዚሁ የሚርቅ አይደለም፡፡ ጠቅላይ ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ስልጣን ላይ ከወጡ ከመጋቢት 24/2010 በኋላ በአገራችን እየሆኑ እና እያለፉ ያሉ ሁነቶች በአግባቡ ትርጉም ለመስጠት ሁሉ ፋታ ነስተውናል ብል ማጋነን አይሆንም፡፡ በዚሁ ላይ በተለያዩ የመገናኛ ብዙሃኖች እና ማህበራዊ ሚዲያዎች የእኛን አእምሮ እና ቀልብ ለመሳብ የሚለቀቁት ትንታኔዎች ወጀብ የተሳፈርንባትን ታንኳ ይበታትናት ይሆን እያልን ባትተናል፡፡

በአንድ ወቅት ላይ በቋንቋ፣ ብሔር፣ ባህል፣ የክልል ድንበር የማይመሳሰሉ በመተሳሰብ ቆመው የእርሱ ደም ደሜ ነው የተባባሉ ወጣቶች አሁን እንደድሮው መተሳሰባቸው ጠፍቷል፡፡ አንድ ቋንቋ፣ ብሔር፣ ባህል እና የክልል ድንበሮች የሚጋሩ ህዝቦች ደም ተቃብተው በየጎጣቸው ውስጥ መወሸቃቸው የአደባባይ ሚስጥር ነው፡ ፡ ኢትዮጲያ አንድ ልታደርገን ብቁ አይደለችም፣ ብሔራችን ይበቃናል ያሉትም፣ ብሔራቸው አልበቃ ብሏቸው ተከፍለው በአንድ ወቅት

ያላንተ አይሆንልኝም ያለውን ወንድሙንና እህቱን በማጠልሸት፣ በማንኳሰስ፣ አካላዊ ጥቃት ለማድረስ በማድባት ተጠምደዋል።

የኢትዮጲያውያን ነገር ፍፁም እንግዳ ሆኗል። አገራችን ኢትዮጲያ እና ነዋሪዎቿ የበርካታ ፀጋዎች ባለቤት ቢሆኑም በየትኛውም የእድገት መመዘኛዎች እጅግ ኋላ ቀሮች ነን። የአገራችን አብዛኛው ነዋሪ ድሃ አርሶ አደርና አርብቶ አደር ነው። ይህ ነዋሪ የራሱን፣ የእርሱን እና የአገሪቷን አስቀያሚ ገፅታ ያስውብልኛል ብሎ ያስተማራቸው ሊሂቃኖች እንኳ ሊያስዉቡ ቀርቶ አገሪቷን በማፍረስ ቁጥር አንደኛ ሚርተኞች ሆነው አርፈዋል። ሚርታቸው አልበቃ ብሏቸዋል መሰል፣ ለማፍረስ ቆርጠው ተነስተዋል። እንደ በርካቶች አስተያየት ኢትዮጲያ እንደ ሊሂቃኖቿ ከሆነ ከፈረሰች ቆይታለች፤ እንደ አገር ያቆያት ህዝቡ ነው። በእርግጥም እንግዳ ጊዜ!

መሬት ላይ ባለው ሁነት ኢትዮጲያችንም ብሄሮቻችንም እያኖሩን አይደሉም። የትኛውም አይነት ብሔርተኝነት ወድቋል። ሊሂቃኖቻችን ማመን ባይፈልጉም- ለስልጣን ይጠቅማቸዋልና- በእርግጥ የብሔርተኝነት አስተሳሰብ ከከሸፈ ቆይቷል ተብሎ መከራከር ይቻላል፡ ፡ አሁን እየኖርንባት ያለችውን ኢትዮጲያ ተመልከቱ፣ በብሔርተኝነት አስተሳሰብ አንድን አገር እንደ አገር ሊያቆማት በሚችሉ መስፈርቶች በሙሉ አገሪቷ መፍረስ ነበረባት። ነገር ግን አልፈረሰችም። ለምን? ብሎ መጠየቅ አስፈላጊ ነው። በብሔርተኝነት አስተሳብ አንድን አገር ያቆማሉ የሚባሉት አላባውያን በእርግጥ አገር ያቆማሉን? አንድን አገር እንደ አገር ለማቆም የእውነት አስፈላጊው/ዎቹ ነገር/ሮች

ምንድን ነው/ናቸው? እነዚህ የብሔርተኝነት አላባውያን ለንፁስ ብሔርተኝትም ይውላሉ። ንዑስ ብሄርተኝነታቸውንስ ያቆምላቸዋል?

ብሔርተኝነት በዓለም ዙሪያ፣ በተለይ በኢትዮጲያ ከገጠመው የተግባራዊነት ፈተና በተጨማሪ ምክንያታዊ ፈተናውንም ማለፍ የሚችል አይደለም። ለምሳሌ ለኦሮሞ፣ የአማራ፣ የሶማሌ፣ አፋር፣ የትግሬ ወ.ዘ.ተ ብሄርተኝነት ትክክለኝነት ምክንያት ማቅረብ አይቻልም። ለኢትዮጲያኑም። በአሁኑ ወቅት ባለው ተጨባጭ፣ ከኢትዮጲያ ብሔርተኝነት እና ከንዑሶቹ ብሔርተኞች የትኛው በርካታ ተከታይ እንዳለው አይታወቅም። ሆኖም አንዳቸው በሌላው ላይ የበላይ ለመሆን እየታገሉ ነው። በምን ምክንያታዊ የትክክለኝነት መስፈርት ነው አንዱ በሌላው ላይ የበላይ የሚሆነው? ለዚህም መልስ አናገኝም።

እንደ አንድ ኢትዮጲያዊ፣ ከተለያዩ ብሔሮች እንደተወለደ፣ በቤተሰቡ፣ በአስተዳደጉ እና በአካባቢው የተለያዩ ብሔሮች እንደኖረ[1] በርግጥ እኛንም፣ ብሄራችንንም ሆነ ኢትዮጲያችንን እያኖረ ያለው እውነተኛ ነገር/ነገሮች ምንድን ናቸው? ሊሂቃኖቻችን በስንት የዕውቀት፣ የድርጅት፣ የገንዘብ ብቃት ሊለያዩን ያልቻሉበት ምክንያት ምንድን ነው?

---

[1] የቤተሰቦቼን የብሔር ተዋጽኦ ለመዘርዘር፡ አማራ (ጎንደርና ወሎ)፣ ኦሮሞ (ሜታ)፣ ጉራጌ፣ ትግሬ፣ ወርጂ (ትግሬ)፣ የሃይማኖት ተዋጽኦ ደግሞ እስልምና፣ ክርስትና (ካቶሊክ፣ ኦርቶዶክስ እና ፕሮቴስታንት)፣ የማከብራቸውና የምወዳቸው ጓደኞቼ አማራ፣ ኦሮሞ፣ ትግሬ፣ ሐረሪ፣ ወርጂ እና ሌሎች ብሄራቸውን የማላውቃቸው…

ለነዚህ ጥያቄዎች መልስ ከየት አገኛለሁ? ከሁለት መቶ ዓመታት በፊት አንድ ብልህ ሰው ስለዚህ ዘመን ሲናገር፣ በተለያዩ ጉዳዮች ላይ የሚፃፉት መፅሐፍት በርካታ ከመሆናቸው የተነሳ፣ አስቸጋሪው መፅሐፍቱን ማንበብ ሳይሆን መፅሐፍቱን መፈለግ ነው ብሎ ነበር፡፡ በርግጥም ልክ ነበር፡፡ ከላይ እንጠቀስኩት ዓለማችን አእምሯችን እና ልባችንን ለመቆጣጠር በሚጥሩ በርካታ ትርጉሞች ተሞልታለች፡፡ እነዚህ ትርጉሞች እርስ በእርስ ከመጋጨታቸው በላይ ቋሚም አይደሉም፡፡ በዚህ ማዕበል ውስጥ በሁለት እግሮቼ ተረጋግቼ እንድቆም የሚያደርገኝ መልህቁ እስልምና- ቅዱስ ቁርአን፣ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ)፣ ቤተሰቦቻቸው እና ልምዳቸው- ነው፡፡

በዚህ ላይ፣ አገራችን ኢትዮጲያ በእስልምና የጥንስሱ ወቅት ላይ ውለታ ውላለታለች፡፡ አሁን አገራችን በዚህ ጭንቅ ወቅት እስልምና በተራው ውለታ ሊውልላት ይገባል ብዬ አምናለሁ፡፡ በኢትዮጲያ እና እስልምና መሃከል ያለው ውለታ ከጅምሩ ለዘመናት የቆየ ነው፡፡ አንዱ ሌላውን ሲያዳብር ቆይቷል፡፡ አሁን እየጠየቅሁ ያለሁት ጥያቄ በረጅሙ ከቆየው የታሪክ ቆይታ አሁናዊ ዘለበቱን ነው፡፡

እስልምና ለዓለማችን/ለህይወታችን ጥያቄዎች መፍትሄ አለው ሲባል ሰምታችኋል፡፡ አንድ ምሁር ጥያቄዎቹ ምንድን ናቸው ሲል ጠይቆ ነበር፡፡ ጥያቄዬ ከላይ እንዳያችሁት ይመስላል፡፡ እንደ አንድ የእስልምና ሃይማኖት ተከታይ መልሶቼን ከየት እንደምፈልግ ግልፅ ነው፡፡ የገጠመኝ ነገር ግን…

ብሔርተኝነት በእስልምና የቅርብ ጊዜ ታሪክ ነው ያለው። እንደ አውሮፓ አቆጣጠር በ1924 የዑስማንያ አፄ ግዛት ከፈረሰ በኋላ ነበር ታሪኩ የሚጀምረው። ታሪኩ እንደ አውሮፓውያኑ ረጅም አይደለም። በሙስሊሞች ልብ ውስጥ ቦታ የለውም። እንደ ችግር ታይቶ ስለማይታወቅ በዚህ ጉዳይ ላይ የተፃፉ ፅሑፎችን ማግኘት ከባድ ነበር። በጣት ነው የሚቆጠሩት- ፈሪድ ኢስሀቅ (2006)፣ The Quran, Liberation & Pluralism፤ ዶ/ር ዓሊ ሙሐመድ (1985)፣ Islam and Nationalism፤ አያቶላህ ሙርተዳ ሙጠሃሪ፣ Western Nationalism and Islam ዶ/ር ኖር ዘማን፣ ዶ/ር ሰዒድ ነዒም፣ ዶ/ር ኸፋይት ዑላህ (2012)፣ Islam and Nationalism: A Contemporary View እና ኢንሳይክሎፒዲያ ኦፍ ኢስላም።

እስልምና ተፈጥሯዊ ሃይማኖት ነውና ለመሠረታውያኑ ነገሮች አትኩሮት ይሰጣል። አንድ የአስተሳሰቡ ተከታይ የትም ተገኝ የትም እንዴት ከራሱ፣ ከሌላ መሰል ሰው፣ ከጎረቤቶቹ፣ ከብሄሩ፣ ከአገሩ፣ ከተፈጥሮው፣ በዐይን ከማይታዩት ረቂቅ ፍጡራን ጋ- ከመልአክትና አጋንት ጋ- እንዴት በሰላም እንደሚኗኗር መንገዱን የሚያሳይ ሃይማኖት ነው። አገር የሚቆሙት ሆነ የሚያፈርሱት እነዚህ መሠረታዊ ነገሮች ሲናጉ፣ ሚዛን ሲስቱ ነው።

በዚህች አጭር ጉዞዬ የተረዳሁት ነገር መሠረታዊ በሆኑ ነገሮች ላይ ከማተኮር ይልቅ፣ በድንገቴ ነገሮች ላይ ጊዜያችንን እያጠፋን እንደሆነ ይሰማኛል። የሊሂቃኖቹን ጫጫታ ወደ ጎን ብለን የምር እኛን ሆነ አገራችንን እያኖረን ያለው ነገር ስናይ ይህን እውነት እንረዳለን።

* * *

ይህች መፅሐፍ የእስልምናን እና ብሔርተኝነትን ትስስር ሙሉ ለሙሉ ዳሳለች የሚል ቅዠት የለኝም። ለውይይት መነሻ የሚሆን ሃሳብ ነው ለማቅረብ የሞከርኩት። በዚህ ጉዳይ ላይ ወደፊት በርካታ ውይይቶች ሊደረጉ እንደሚችሉ አምናለሁ። ህዝባችን ከየትኛውም ማንነት ይገኝ ይህቺን አገር እያቆያት ያለው እርሱ ነው። ምክንያቱ ደግሞ ግንኙነቶቹን መሠረታዊ፣ ምክንያታዊ እና ተፈጥሯዊ ነገሮች ላይ ስላደረገ። እነዚህ መሰረታዊ የአንድነት አላባውያን ላይ እንድናተኩር ለመግፋት ነው። በሌላ አባባል፣ ሊሂቃኖቹ የእርሱ አገልጋዮች እንዲሆኑ ማድረግ ነው። እነርሱም በአፋቸው በተደጋጋሚ እንደተናገሩት፣ ከማልማት ይልቅ ጥፋት ላይ የተሰማሩትን ሊሂቃኖቹን ለምን ይከተላል? እነርሱ ናቸው እኮ እርሱን መከተል ያለባቸው፣ ቢያንስ አገርን በማቆየት ረገድ። ሊሂቃኖች በሙሉ የተበላሹ ናቸው ብዬ አክራሪ ልሙጥ አቋም መያዝ አልፈልግም። ነገር ግን የህዝብ አገልጋይ መሆን አለባቸው ብዬ ግን አቋም ይዤለሁ።

በመጨረሻም፣ ይህችን መፅሐፍ እያነበባችሁ ከሆነ ሃያ አምስት የኢትዮጲያ ብር (25.00) እንደከፈላችሁ እርግጠኛ ነኝ። በኢትዮጲያ ህዝብ ተስፋ መቁረጥ አልፈልግም፤ በብዙ ፈተናዎች ውስጥ ቢሆንም አሁንም ጨዋ እና ሃይማኖተኛ እንደሆነ አምናለሁ። ይህን እና ሌሎች መፅሐፎቼን በድፍረት በሶፍት ኮፒ እንድለቅ ካደረጉኝ

ምክንያቶች መሃከል አንዱ እና ዋናው ይህ ነው፡፡ እናም በሚከተሉት የባንክ አካውንቶች ብሩን በስሜ አስገቡልኝ፡፡

የኢትዮጲያ ንግድ ባንክ፡ ዐቢይ ጣሰው- 1000095979258

የአዋሽ ባንክ፡ 01320089003300

በዚህች ጉዞዮ በርካቶች ከጎኔ ነበራችሁ፡፡ አጠገቤ ካሉት ቤተሰቦቼ እና ጓደኞቼ ጀምራችሁ፣ የፌስ ቡክ ጓደኞቼ ሳትቀሩ ውለታችሁ ተዘርዝሮ የማያልቅ ከፍተኛ ነው፡፡ ሁላችሁንም አመሰግናለሁ፡፡ በተለይ ባለቤቴ ሙና እሸቱ እና እህቷ ሐናን እሸቱ፤ ጀማል ካሳሁን፤ ሰልዋ ፍቃደ፣ ኤልያስ እሸቱ፣ አሊያ ሐይደር፣ ቢኒያም ጣሰው በዋናነት ይጠቀሳሉ፡፡ አመሰግናለሁ!

መፅሐፏ ማስታወሻነቷ ወርቋማውን ህግ ለሚከተሉ እና ህያው ለማድረግ ለሚጥሩ ትሁንልኝ!

## ምዕራፍ አንድ፡ የብሔርተኝነት ታሪክ ቅኝት

### *ብሔርተኝነት እንደገዥ ሃሳብ*

ምንም እንኳ የብሔርተኝነት የተወሰኑ ባህሪያት ከበርካታ ሺህ ዓመታት በፊት በቀደምት የግሪክ ጎሳዊ ከተማ መንግሥት (city-state) ቢታዩም፣ ብሔርተኝነት እንደ ፓለቲካ፣ ማህበራዊ እና የአስተሳሰብ ትምህርት ቤት ርዕዮተ ዓለም የተወለደው የፈረንሳይ አብዮትን ተከትሎ ነበር።

ጃን-ጃኪውስ ሩሶ የዚህ ገዥ ሀሳብ ቀንደኛ አቀንቃኞች መሃከል ዋናው ነበር። ለሠፊው ህዝብ አንድነት፣ ወንድማማቾነት እና የቡድነኝነት/ስብስብ መንፈስ አፅዕኖት በመስጠት አንድ ሰው ለቆዬውና ላደገበት አገር ከፍተኛ ቁርኝት ሊኖረው ይገባል ሲል መክሯል። የግለሰብና የስብስብ ፍቅር እና ታማኝነት ማጠንጠኛው አባት አገር መሆን አለበት ብሎ ያምናል። ይህን እምነቱን ወደ ቅዱስ ሃላፊነት ከፍ አድርጎት ከዚህ ውጭ ያሉ ስብስቦች እና ሃይማኖታዊ የህብረተሰብ አደረጃጀቶችን ኮንኗል።

የብሔርተኝነት አስተሳሰብ ትምህርት ቤት ዋና መሰረት የተጣለው በፈንሳዩ አብዮት ሲሆን፣ ለመጀመሪያም ጊዜም ተግባር ላይ የዋለው በዚያው ነበር። ለባንዲራና አገር፣ ብሔራዊ ጀግኖችን የማላቅና የማምለክ ስሜት፣ ብሔራዊ ህዝበ-መዝሙር ማዘጋጀት፣ የፈረንሳይ ቋንቋ እና ዘር ጥብቅነትን ማጽናት፣ በሃይማኖታዊ አምልኮ መንፈስ

ታላላቅ ብሔራዊ ፌስቲቫሎችንና ባህሎችን መፍጠር፣ በፈረንሳይ ታሪክ መኩራት እና በፈንሳይ ህዝብ ታላቅ ተልዕኮ ማመን በአብዬቱ እየተገለጡ እና አንዱ ሌላውን እየተከተለ ህያው ሆኑ፡፡ በጃኮቢኖች ወደ ስልጣን መምጣት እና አብዮቱን ተከትሎ የመጣው ጥፋት፣ የብሔርተኝነት ክፋቶች ከጅምሩ መታየት ጀመሩ፡፡ ለእነርሱ ብሔርተኝነት በሰፊው ህዝብ ስሜቶች ላይ መጫወቻ፣ በጎረቤት አገሮች ላይ ጥቃት ለማድረስ፣ ተስፋፊነት፣ ጅምላ ግድያ፣ ሙስና፣ ጭቆና እና የሊሂቃን ጥቅም ማስጠበቂያ መሳሪያ ነበር፡፡ የብሔርተኝነት ስሜት መገለጫው ጥቃትና ቅኝ ግዛት ሆነ፡፡ ለእነርሱ የፈረንሳይ ጥቅሞች የውሳኔዎችን መሰረት ነበሩ፡፡

የፈረንሳይ አብዮት ተፅዕኖ መስፋፋትን ተከትሎ በምዕራቡ ዓለም የብሔርተኝነት ፅንሰ ሀሳብ፣ የነጻነት እና ዲሞክራሲ ሃሳቦችን እየተካ መሬት ቆንጥጦ መያዝ ጀመረ፡፡ የናፓሊዮን ቦናፓርት መነሳት ፍጥነቱን ይበልጥ ጨመረው፡፡ ናፓሊዮን የ”ብሔርተኝነት ገዥ-ሃሳብ መሆን” አክራሪ ደጋፊ ሲሆን ወደፊት እንደምናየው በእስልምናውም ዓለም የለኮሰው እርሱ ነበር፡፡ ለብሔርተኝነት ያለው ጠንካራ ስሜት ለተስፋፊ እና ተንኳሽ ፓሊሲዎቹ መሠረት ጥለዋል፡፡ የከፈታቸው ጦርነቶች፣ የፈፀማቸው ዕልቂቶች በፈንሳይ ህዝብ ውስጥ የበላይነትን መንፈስ አነቃቅቷል፡፡ ሌሎች አገራት ይህን መንገድ ለመከተል ብዙም ጊዜ አልፈጀባቸውም፡፡ በጀርመን እና ጣሊያን የብሔርተኝነት መንፈስ ህያው የሆነው ወዲያውኑ ነበር፡፡ በዚሁ የብሔርተኝነት ስም አሰቃቂ ወንጀሎች ተፈጽመዋል፡፡ ለስልጣን አእላፍ ጨራሽ ትግል ተጀመረ፡፡

አስራ ዘጠነኛው መቶ ክፍለ ዘመን ለብሔርተኝነት ወርቃማ ዘመን ነበር፡፡ በዚሁ ዘመን ቶማስ ጀፈርሰን እና ቶማስ ፔይን ለአሜሪካ ብሔርተኝነት መሠረቱን ጣሉ፡፡ በእግሊዝን ጄርሚ ቤንተም ለብሔርተኝነት አዲስ አድማስ ሰጠው፡፡ ከዊልያም ግላድስቶን ጋር የእንግሊዝ ብሔርተኝት ወደ ላይ ተተኮሰ፡፡ በመሃከለኛው እና ምዕራብ አውሮፓ በሙሉ ብሔርተኝነት እንደ ምሁራዊ ቅስቃሴና የአስተሳሰብ ትምህርት ቤት ተስፋፋ፡፡ ጣሊያኒያዊው ማዚኒ የ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የብሔርተኝነት የአስተሳሰብ ትምህርት ቤት ንድፈ ሀሳብ ቀማሪዎች መሃከል ዋናው እንደሆነ ይቆጠራል፡፡ በክፍለ ዘመኑ የብሔርተኝነት ሰንደቅ ተሸካሚ ከሆኑት መሃከል ጉሴፔ ጋሪባልዲ ከጣሊያን፣ ቪክቶር ሂውጎ ከፈረንሳይ እና ኦቶ ቢስማርክ ከጀርመን ይጠቀሳሉ፡፡

በጊዜው ብሔርተኝነት ታላላቅ ክስተቶችን ፈጥሯል፡፡ ቢልጅየም ነጻነቷን ተቀዳጅታለች፤ የደቡብና መሃከለኛው አሜሪካ አገራት በሲሞን ቦሊቫር እና ጆሴ ማርቲን መሪነት የፖርቹጋል እና ስፔን ቅኞች ነጻ ወጥተዋል፡፡ ሆኖም እጅግ ጠንካራው የብሔርተኝነት መንፈስ የታየው በኦቶማን ግዛት የአውሮፓ ቅኞች ውስጥ ነበር፤ ግሪክ፣ ቡልጋሪያ፣ ሃንጋሪ፣ ፊንላንድ፣ ቸኮዝሎቫኪያ፣ ክሮሺያ ነጻነታቸውን ለመቀዳጀት ሞክረዋል፡፡

በርግጥ በሶስተኛው ዓለማት ከታየው ያልተጠበቀ ቅኝ ግዛት መስፋፋት እና በምዕራብያውያን መንግሥታት መሃከል ከተፈጠረው ፓለቲካዊ ግጭቶችና ጦርነቶች አንጻር ሲታዩ ከላይ የተጠቀሱት

ሁነቶች ክብደት አልነበራቸውም። ታሪክ እንደሚያሳየን ብሔርተኝነት ከልማት ጥፋቱ ያይላል። የእንግሊዝና የፈረንሳይ የቅኝ ግዛት ፓሊሲዎች እና ጥቃቶች፣ የናፖሊዮን III እና ቢስማርክ ተስፋፊነት የብሔርተኝነትን አታላይነት እና ደካማ ህዝቦች ለመጨቆን ሽፋን ሰጪነት ያረጋግጣሉ።

## *የብሔርተኝነት ሃሳብ*

ብሔርተኝነት የምዕራቡ ዓለም የርዕዮተ-ዓለም ክፍተቱን ለመሙላት የፈጠረው ሃሳዊ-ሃይማኖታዊ የአስተሳሰብ ትምህርት ቤት ነው።

ሰው ፍቅሩን ወይም ውዴታውን ሊያሳይበት ከሚችለው እምነት ርዕዮተ-ዓለም ውጭ መኖር አይችልም። በመካከለኛው ዘመን የምዕራቡ ዓለም እምነቱን፣ ርዕዮተ-ዓለሙን የሚናገኘው ከክርስትና ሃይማኖት ነበር። ነገር ግን ከተሃድሶው ዘመን ጀምሮ የተነሱትን ዕሳቤዎች ሃይማኖቱ መቋቋም አልቻለም።

የተሃድሶው እና ቀጥሎ የመጡት ለውጦች በክርስትና ሃይማኖት ላይ ከፍተኛ ጥቃት አደረሱ። ክርስትናም በአውሮፓውያን የዕለት ተዕለት ህይወት ውስጥ ህያው እምነት መሆን አልቻለም። ከህዝቡ የፖለቲካ፣ ማህበራዊ፣ ምሁራዊ እና የስሜት ሕይወት ውስጥ እየወጣ በአብያተ ክርስቲያን ግንቦች ውስጥ በመታጠሩ የምዕራቡ ዓለም ውስጥ ከፍተኛ ክፍተት ተፈጠረ።

የምዕራቡ ዓለምን ዳግም ህያው የሚያደርገው ሌላ የሃሳብ ምንጭ በቅርብ ባለመኖሩ ጭለማ ውስጥ ተተወ። ሰው በእንደዚህ አይነት ክፍተት ውስጥ ለረጅም ጊዜ መኖር ስለማይችል የምዕራቡ ዓለም አዛሮች ብሔር የሚባል ጣዖት ቀርፀው ሰጡት። ያ የተጠማ አማኝም አዲሱን ሃይማኖትና ጣዖት ተቀበለው። በኋላ ላይ ማርክሲዝምም የተቀላቀለ ሲሆን፣ እነዚህ ሁለቱ የአስተሳሰቡ ት/ቤቶች ለመፈጠር የበቁት ክርስትና የተወውን ክፍተት ለመሙላት፣ የተጠማውን የምዕራብ ዓለም ህዝብ ለማርካት ነበር።

በተቃራኒው የእስላማዊው ምስራቅ ታሪክ እንደዚህ አይነት ክፍተት አልተሰተዋለበትም። አሁንም በሙስሊሙ ዓለም እስልምና ከሌሎች ርዕዮተ-ዓለሞች በተሻለ በተከታዬቹ ውስጥ የሰብአዊነት አብዮታዊ ስሜት፣ ወንድማማችነትን እና ሃይማኖታዊ መሰጠትን የመቀስቀስ ሃይል አለው። የአስተሳሰቡ ት/ቤት በሚያዘው መሰረት ተከታዬቹ ህይወታቸውን እንዲሰጡ፣ ሃብታቸውን እንዲያፈሱ የማድረግ አቅም ስላለው በዚህ ዓለም ብሔርተኝነት ተረጋግቶ መቀመጥ ያልቻለው ለዚህ ነው። የምስራቁ ዓለም ብሔርተኞች እና በምዕራቡ ዓለም ትምህርታቸውን የቀሰሙ ምሁራን በምዕራቡ ዓለም ተሞክሮ ስኬታማ የሆነን ነገር በህዝባቸው ላይ ለመጫን መሞከራቸው፣ ህዝባቸውን እና አገራቸውን አለማወቃቸው አመልካች ነው። የምዕራቡ ዓለም ጭፍን ገልባጭ ምሁራን በምዕራቡ ዓለምና በሙስሊሙ ዓለም ያለውን ልዩነት እንዳይረዱ አድርጓቸዋል። የሙስሊሙ ዓለም አሁንም በውስጡ ህያውና አብዮታዊ ሃይማኖት እስልምና አለው።

*ብሔርተኝነት እና ቅኝ ግዛት*

ቅኝ ግዛት እና ካፒታሊዝም የብሔርተኝነት መስፋፋት ያገዙ ሁለቱ ግብዓቶች ናቸው፡፡

በአስራ ዘጠነኛው መቶ ክፍለ ዘመን የምዕራቡ ዓለም ሶስተኛውን ዓለም በቅኝ ለመግዛት እና ለመመዝበር አስፋሪ ፉክክር ውስጥ የገባበት ነበር፡፡ የአፍሪካ እና ኤስያ ህዝቦች ላይ እንደ ተራቡ ተኩሎች ተወረወሩባቸው፡፡ ብሔርኝነት ለዚህ አስፈሪ ወንጀላቸው መሸፈኛ ጭንብል እና ተጨማሪ የብዝበዛ ፍላጎታቸውን ይሁንታ ለማሰጠት ብሔርተኝነት አስፈላጊውን ርዕዮተ-ዓለም ሰጥቷቸዋል፡፡

የብሔርተኝነት አስተሳሰብ ት/ቤት ከቅኝ ግዛት ጋ በተያያዘ በሶስት ደረጃዎች የተከፈሉ አስፈላጊ ሚናዎችን ተጫውቶላቸዋል፡፡

1. የቅኝ ግዛት ምንጭ ሆኗል፡፡ ከብሔርተኝነት ምንጭ የተቀዱት የብሔር እና ዘር የበላይነት፣ የጎሳ ኩራት፣ የራስን ታሪክና ባህል መቀደስ ለፓለቲካዊ ተስፋፊነትና በራስ ጥቅም ዙሪያ ለሚሽከረከር ኢኮኖሚያዊ ጥቅም መሠረት ጣለ፡፡ ኢምፔሪያሊዝም ከዚህ የብሔርተኝነት ክፉ ሽንት የተወለደ ኢ-ህጋዊ ልጅ ነው፡፡

2. ብሔርተኝነት “በብሄራዊ አስፈልጎት” እና “የአገርን ታላቅነት ህያው ማድረግ” በሚል ሽፋን የምዕራቡን ዓለም ቅኝ ግዛት እና ነውረኛ ድርጊቶች ቅቡል አድርጓል፡፡

3. የብሄርተኝነት መንፈስ ያስጠበቀ ጠንካራ መግፍኤ ሆኖ አገልግሏል። ለአባት አገር መስዋዕት መሆን በሚል መንፈስ እና የተወጠረ ብሄራዊ ስሜት በማቀጣጠል የቅኝ ግዛት መግፍኤ ዘርግቷል፤ እንግሊዝ፣ ፈረንሳይ እና ጀርመኖች አፍሪካን እና ኤስያን ለመቀራመት እርስ በእርስ ባደረጉት ትንቅንቅ ጉልበት ሆኗቸዋል።

ታዋቂው የምዕራቡ ዓለም አብሰልሳይ ፍራንሲስ ኩከር ሲጽፍ “በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን በርካታ ብሔርተኞች ከአክራሪ የብሄርተኝነት መንፈሳቸው በመነጨ የበለጸጉ ህዝቦች ምጡቅ ታሪክና ባህል፤ የዘርና ብሔር ’በላይነት አላቸው ብለው ያምኑና ይናገሩ ነበር፡ ፡ ስለዚህ ችሎታቸውን በድንበሮቻቸው አጥረው መቀመጥ ወንጀል ሆኖባቸዋል። የብሔርተኝነትና አርበኝነት ሃላፊነታቸው ድንበሮቻቸውን በመከላከል እና ነጻነታቸውን፣ የአገራቸውን ሉዓላዊነት በመጠበቅ መገደብ የለበትም። የፓለቲካዊ እና ባህላዊ ተጽዕኖ ክልል ለሰው ልጆች ጥቅም ሲሉ ሞላ ዓለምን እንዲያካልል፤ እንዲሁም ያልለሙ መሬቶች እና ነዋሪ ህዝቦቻቸውን በሃይል፤ አስፈላጊም ከሆነ በአካላዊ ቅጣት የማሰልጠን ዓለም አቀፋዊ ተልዕኮ ነበራቸው።”

የብሔርተኝነት አመክኗዊ መደምደሚያ የሆነው ከላይ የተነሳው ዕይታ፣ የቅኝ ግዛት መሠረትን እና የኢምፔሪያሊዝምን አሰቃቂ ብዝበዛ ህጋዊ ያደረገ ነበር።

የ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የብሔርተኝነት አስተሳሰብ ት/ቤት መስራቾች ጽሑፎች እና የቃላት ቅኝት፣ የብሄርተኝነታችን ሃላፊነት ዳር ድንበራችንን በመጠበቅ ብቻ መወሰን የለበትም፤ ለአገራችን ታላቅነት ስንል በሺዎች በሚቆጠሩ ኪሎ ሜትሮች ርቀው በሚገኙ ህዝቦች ላይ ፓለቲካዊ እና ወታደራዊ ሃይላችንን ማሳየት አለብንን ሃሳብ በትጋት ሲያስተጋቡ እንደነበር ያሳያል።

የዚሁ ክፍለ ዘመን ብሔርተኛ አብሰልሳይ ዶ/ር ብሪጂሄት ሲጽፍ “በአገራዊ አንድነታችን ብቻ መወሰናችን በቂ አይደለም፤ ከዓለም አቀፉ የፓለቲካ እና ወታደራዊ ሩጫ ወደኋላ መቅረታችን የአገራችንን ታላቅነት የመጠበቅ ሃላፊነታችንን መዘንጋት ነው። ከመስፋፋት ከታቀብን ብሔራዊ ኩራታችን ይጎዳል። ጉጉ እና ጠረኞች በመሆን ብቻ ነው ብሔራዊ ኩራታችን የሚጠበቀው።”

ብሔርተኝነት የዳርዊንን ሃያሎች ይኑሩ ምልከታ ወደ ፓለቲካዊ እና ማህበራዊ አውድ አምጥቶታል። ኤርነስት ሄይክል ሃሳቡን በጀርመን እንዲህ ሲል አስተዋውቆታል- ጠንካራ እና ሃያል ህዝቦች ብቻ የመኖር እና ደካማና ጎታታ ህዝቦችን የመዋጥ ሙሉ መብት አላቸው። ይህንን “የዘመናዊው ስልጣኔ ጥቅል አውሬነት” ብለን ልንጠራው እንችላለን። ካርል ፒርሰን- ሌላው ታዋቂ ብሔርተኛ- እንዲሁ የዳርዊን ምልከታ “በህዝቦች መሃከል ያለ ተፈጥሮዋዊ ግንኙነት” እንደሆነ ወስዶታል።

በእንደዚህ አይነት የብሔርተኞች መከራከሪያ ምክንያት በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ከዚያ ቀደም ታይቶ የማይታወቅ ገብጋባ

ተስፋፊነት ታይቷል፡፡ በእንግሊዛዊው ብሔርተኛ ግላድስቶን የተመራው ቅኝ ግዛት ህንድንና የዓለማችንን በርካታ ክፍሎች ውጧል፡፡ ጀርመንም በብሔርተኛዋ ቢስማርክ የራሷን ድርሻ ወስዳለች፡፡ ፈረንሳይ የአፍሪካን የተለያዩ ህዝቦች ወርራ ቅኞቿ አድርጋቸዋለች፡፡ እንግሊዝ የስዊዝ ክፍልን ይዛ የኢምፔሪያሊዝም ምኞቷን አስፍታለች፡፡ ጀርመን ከበርሊን እስከ ባግዳድ የተዘረጋ የአርያን አጼ ግዛት የመፍጠር ምኞት ነበራት፡፡ እንደ አዲስ የሃያሎቹን ጎራ የተቀላቀለችው አሜሪካ ራሷ ፊሊፒንስን እና ሩቅ ምስራቅ አገራትን ይዛለች፡፡ የቅኝ ግዛት ጥም ያቃጠላቸው ፈረንሳይና ጀርመን ሞሮኮን ለመቆጣጠር ግጭት ውስጥ ከቷቸዋል፡፡ ተመሳሳይ ግጭት በሩሲያ እና በእንግሊዝ መሃከል ተነስቶ ነበር፤ አገሪቷ ኢራን ነበረች፡፡ እነኚህ ሁሉ የብሔርተኝነት እንግዳ ውጤቶች ነበሩ፡፡

የህብረተሰብ ታሪክ ፀሐፊው ጆሴፍ ላይትን ይህን ጽፏል፡

“የ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ታሪክ በሙሉ በኢኮኖሚያዊ-ፓለቲካዊ ብሔርተኝነት እና በቅኝ ግዛትና ግጭት ውጤት ላይ ቆሟል፡፡ ብሔርተኝነት የተለያዩ መንግስታት ለፈፀሙት ተስፋፊነት እና ፍትኒያ መሠረቱ ነው፡፡” የተወሰኑት የዚሁ ክፍለ ዘመን ታዋቂ ብሔርተኞች ለአስፈሪ ቅኝ ግዛት መስፋፋት እና የታሪካችንን ታላላቅ ወንጀሎች ዋና አቀጣጣዮች ነበሩ፡፡

በዚህ ረገድ ግላድስቶንን የሚወዳደረው የለም፡፡ እንደ የእግሊዝ ቅኝ ግዛት ሰንደቅ ያዥነት በደካሞቹ የሶስተኛ ዓለም ህዝቦች ላይ አስቃቂ ጥቃት አድርሶ ቀንበሩን ጥሎባቸዋል፡፡ ሮበርት ክሊብ ቅኝ ግዛቱን

ወደ ህንድ አስፋፍቶ በፔላሲ ጦርነት ህንዶችን ጨፍጭፏል፡፡ ሴሲል ጆን ሮድስ እንዲሁ ወደ ተቀረው ቦታ ተስፋፍቷል፡፡ እነዚህ ሁሉ ሰዎች የአውሬ እና ነውረኛ ተግባራቸውን ህጋዊ እና ቅቡል ያደረጉት በብሔርተኝነት ስም ነበር፡፡

## *ብሔርተኝነት በ20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን*

የ20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የብሔርተኝነት ታሪክ በሁለት ክፍለ ጊዜያት ይከፈላል፡ ሀ/ የመጀመሪያው ግማሽ ብሔርተኝነት እና ለ/ የሁለተኛው ግማሽ ብሔርተኝነት፡፡

እስከ ሁለተኛው የዓለም ጦርነት ድረስ ያለው የ20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የመጀመሪያው ግማሽ የብሔርተኝነት ታሪክ በአውሮፓና በሩቅ ምስራቅ ኤስያ (ጃፓን) ዓለም አቀፍ ጦርነቶችን በማድረግ ምንነቱን ገልጧል፡፡ ቅኝ ገዢዎች ዓለምን በሙሉ በቁጥጥራቸው ስር የማድረግ ህልማቸው አላስቆም አላስቀምጥ ብሏቸዋል፡፡ ይህም ሁለት አውዳሚ ጦርነቶችን እንዲዋጉ አድርጓቸዋል፡፡ በርካታ ምሁራን የመጀመሪያውና የሁለተኛው ዓለም ጦርነቶች ዋና መንስኤ የብሔርተኝነት ስሜት መሆኑን አምነዋል፡፡ በዚህ ዘመን የብሔርተኝነት እውነተኛ ልጆች የሆኑትና አስተሳሰቡን ከፍተኛ ማማ ላይ ሰቅለው እውነተኛ አስቀያሚ ገጽታውን ያሳዩን የጣሊያኑ ሞሶሎኒ፣ የጀርመኑ ሂትለር፣ የአርጀንቲናው ፔሮን፣ የስፔኑ ፍራንኮ እና የፓርቹጋሉ ሳላዛር ነበሩ፡፡ እነዚህ የብሔርተኝነት ህሱም ውጤቱ

ሲሆኑ አሁንም ብሔርተኝነት እርጉም ምርቱን ከመስጠት አልተቆጠበም፡፡

በሁለተኛው አጋማሽ ብሔርተኝነት የታየው በሶስተኛው ዓለም ውስጥ ነበር፡፡ መጀመሪያ ቅኝ ግዛትን ከአህጉሩ ለመንቀል የተደረገ ቅስቃሴ ቢመስልም፣ ቀረበ ብሎ ለመተመለከተው ግን ሙሉ ታሪኩን ማየት ይችላል፡፡ የምዕራቡ ዓለም ባህልና የበላይነት ከምስራቁ ዓለም ባህል፣ አስተሳሰብና አጥባዊ ልማዶች ጋ ተቃራኒ በመሆኑ በቅኝ አገዛዝ ላይ አመፅ መቀስቀሱ የማይቀር ነበር፡፡ ህዝቡ ለአመፁ መግፍኤ በዋናነት ሃይማኖትና ሃይማኖታዊ ስሜት ሲሆን የብሔርተኝነት ሃሳብ እና ስሜት አልነበረውም፡፡ የተወሰኑ ባለብሩህ አዕምሮ ባለቤቶች ቀጥታዊ ቅኝ ግዛትን እና ተፅዕኗቸውን እንደቀድሞው ማስቀጠል እንደማይችሉ ሲገባቸው ተቋውሞው በብሔርተኝነት ስም እንዲካሄድ አቅጣጫ አስለወጡ፡፡ በዚህ መንገድ ምንም እንኳ ቅኝ ገዥዎቹ ቦታቸውን ለቀው ቢወጡም ዕሴቶቻቸውንና የገዥነት መንገዳቸውን ያስጠብቃሉ፡፡

በአሁኑ ዓለም ቅኝ ግዛት ያለፈ ታሪክ ቢሆንም፣ ቅኝ ተገዥዎችም ነጻነታቸውን ቢቀዳጁም፣ በቅኝ ገዢዎች ጥቅም ላይ የዋለው ብሔርተኝነት አሁን ሚናው በተወሰነ መልኩ ተለውጧል፡፡

ድህረ ቅኝ ግዛት ብሔርተኝነትን በመጠቀም ቀድሞ አንድ የነበሩ ህዝቦች አንድነታቸውን እንዳያገኙ እየከለከላቸው፤ በሃያሉ ላይ ጥገኛ የሆኑ ደካማ እና ጥገኛ አድርጓቸዋል፡፡ የምስራቁ ዓለም ህዝቦች አንድነትና ጥንካሬ በቅኝ ገዥዎች ጥቅሞች ላይ ግልጽና እውነተኛ

አደጋ እንደሚያስከትል ስለተረዱ፣ ህዝቦቹ ተዳክመው እንዲቀሩ ብሔርተኝነትን ወደ ምስራቁ ዓለም በመላክ በአዲሶቹ የአፍሪካ እና ኤሲያ አገራት መሃከል ግጭቶችን ያራግቡ ነበር፡፡ በዚህ መንገድ በመሃከላቸው የጠላትነት መንፈስ እንዲገነግን በማድረግ አንድነታቸው እና ወንድማማችነታቸው እንዳይጠበቅ ይቆጣጠራሉ፡፡ ቅኝ ገዥዎች በወጡበት ቦታ ሁሉ የአገሪቱ ጉዳዩች በሙሉ የሚተዳደሩት በምዕራቡ ዓለም በተማሩ የተወሰኑ ሊሂቃኖች ሲሆን፣ ብሔርተኛ ሃይሎች ሃይማኖታዊ ሃይሎችን እንዲጋፈጡ ይበረታታሉ፡፡ በብሔርተኝነት እና ቅኝ ግዛት መሃከል ያለው ትስስር አሁንም የተጠበቀ ሲሆን፣ ብሔርተኝነት ቅርንጫፉ በታየበት ቦታ ሁሉ ኤምፔሪያሊዝም ስሩን የምናገኘው በዚህ ምክንያት ነው፡፡

## ምዕራፍ ሁለት፡ ብሔርተኝነት በእስልምና ዓለም ውስጥ

### *ብሔርተኝነት እንግዳው ትምህርት ቤት*

ብሔርተኝነት የሙስሊሙን ዓለም አንድነት ለመረበሽ በበዝባዥ ሃይሎች ወደ ውስጥ ሲወረወር የኖረ እንግዳ የአስተሳሰብ ትምህርት ቤት ነው፡፡ የምዕራቡን ዓለም የፓለቲካና የባህል ቅኝ ግዛት ወደ አፍሪካ እና ኤስያ ለማስተዋወቅ ሲሠሩ የነበሩት የተወሰኑ አብሰልሳዮችና ምስራቅያውያን (Orientalists)፣ አሁንም አስተሳሰቡ እንዲስፋፋ እና የአስተሳሰቡ ሰንደቅ ተሸካሚ የሆኑት የተበራዩ ስብሰቦች የሚባሉት እንዲነሱ ምቹ ሁኔታዎች ፈጥረዋል፡፡

የምዕራቡ ዓለም መንግሥታት "ፓን ኢስላሚዝም" ብለው የሚጠሩት የሙስሊሙ ዓለም አንድነት ለፓለቲካዊ እና ኢኮኖሚያዊ ጥቅማቸው እንደ አደጋ ነው የሚቆጥሩት፡፡ በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን በሰይድ ጀማል አል-ዲን እና ሱልጣን አብዱልሐሚድ አነሳሽነት "ስለሙስሊሙ ዓለም አንድነት" ቅስቃሴ ለመፍጠር ሙከራ አድርገው ነበር፡፡ በዑስማንያ አጼ ግዛት ውስጥ የነበረው የቱርኮችና የዐረቦች አንድነት፣ ቁልፍ ወደሆነው የመካከለኛው ምስራቅ ክልል የምዕራቡ ዓለም ዕሴቶችና አስተሳሰቦች ዘልቀው እንዳይገቡ አግዶ ይዞ ነበር፡፡

ቅኝ ገዥ ሃይሎች የዚህ ሙከራ አደጋ ስለታያቸው አደናቃፊ ፓሊሲ አዘጋጁ፤ በሚያሳዝን ሁኔታ ስኬታማ ሆነዋል፡፡ ፓሊሲው በዐረቦችና በቱርኮች መሃከል የብሔርተኝነት ጠንካራ ስሜት መትከል፣ የፓን

ኢስላሚዝምን ኘሮጀክት ማደናቀፍ፣ የታላቁን ዑስማንያ አጼ ግዛትን መከፋፋል እና እየተዳከመ የመጣውን የአጼ ግዛቱን ተጽዕኖ በምዕራቡ ዓለም ቅኝ ግዛት መተካት ነበር፡፡

ብሔርተኝነት በሙስሊሙ ዓለም የተነሳው በእንግሊዝና ፈረንሳይ ተፅዕኖ ስር በነበሩት መሬቶች ላይ ሳይሆን በዑስማንያ አፄ ግዛት ቁጥጥር ስር በነበሩት ውስጥ መሆኑን ማስታወስ ይጠቅማል፡፡ በእንግሊዝ ቅኝ ስር በነረበችው ህንድ እንደ አለቃ ሰይድ አሕመድ ካን ያሉ ምሁራን በብሔርተኝነት አስተሳሰብ ላይ መጠንጠል አላስፈለጋቸውም ነበር፡፡ የሙስሊሙን የትምህርት እና ኢኮኖሚያዊ ይዞታ በማሻሻል ላይ ነበር አትኩሮት አድርገው ሲሰሩ የነበረው፡፡ እንደውም ብሔርተኛውን የሂንዱ ኮንግረስ ፓርቲ ይቃወሙ ሁሉ ነበር፡፡ በአልጄሪያ እና ሱዳንም እንዲሁ፣ በሱዳኑ መህዲ እና በአልጄሪያው አብዱልቃድር ውስጥ ህያው የነበረው እስልምና ነበር፤ ብሔርተኝነት ደብዛው አይታይም፡፡ በፈረንሳይና እንግሊዝ ቁጥጥር ስር የነበሩት ሩቅ ምስራቅ አገራት ውስጥ ያሉት የሙስሊም ምድሮች- በኢንዶኔዥያና ማሌዢያ፣ ምዕራብ ቀመስ ምሁራን እንኳ ለብሔርተኝነት ፍላጎት አልነበራቸውም፡፡

በተቃራኒው ቅኝ ግዛትን ለማስፋፋት የተነሱ ምሁራን የብሔርተኝነትን ጥሪ ያነሱት በዑስማንያ አጼ ግዛት በሆኑት በቱርክ፣ ግብጽ እና ዐረብ መሬቶች ላይ ነበር፡፡ ይህ ታሪካዊ ሐቅ በግልጽ እንደሚያሳየው በሙስሊሙ ዓለም ውስጥ ልባቸው ለብሔርተኝነት የተከፈቱ ሰዎች የነጻነት ትግላቸውን ሲያደርጉ

የነበሩት ከመጤ ጠልነት ጋ የተያያዘ አለመሆኑ ነው። የዑስማንያን አጼ ግዛት አዳክሞ የሙስሊሙን ዓለም ለመበታተን የተነሱ የምዕራቡ ዓለም ክፉ ውላጆች ነበሩ።

ለምን ኢስታንቡል፣ ካይሮና ቤይሩት በብሔርተኝነት ሃሳብ ተጠመዱ? ለምን የቅኝ ገዢዎች መስፋፋት ጣሪያ በነካበት በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን መጨረሻ፣ የብሔርተኝነት ፍቅር በነዚህ የሙስሊሙ ምድር ገነነ? ለምን ዐረቦችና ቱርኮች ፍጥጫ ውስጥ ገቡ? ለምን የብሔርነኝነት ስሜት በዑስማንያ አጼ ግዛት ሲጦዝ በሌሎች የምዕራቡ ቅኝ ግዛቶች ውስጥ ባሉ የሙስሊሞች ምድሮች ቀዝቃዛ ሆነ? ለምን በከፍተኛ የብሔርተኝነት ጡዘት የዑስማንያ አጼ ግዛት መፍረስ ተከትሎ ቅኝ ገዥዎች የመካከለኛውን ምስራቅ መዋጥ ተሳካላቸው?

## *ናፓሊዮን እና ፈረንሳውያን፡ የግብጽ ብሔርተኝነት ተካይ*

ብሔርተኝነት በሙስሊሙ ዓለም የተወለደው በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ሲሆን የመጀመሪያዎቹ ተጠቂዎች ግብጽና ቱርክ ነበሩ። የናፓሊዮን የግብጽ ወረራ የሙስሊሙ ዓለም ታሪክ መጠምዘዣ ነጥብ ሲሆን የምዕራቡ ዓለም ከፍተኛ ተጽዕኖ መጀመሪያ ነበር። ፈረንሳዮች በግብጽ ያደረጉት አጭር ቆይታ፣ የምዕራቡ ዓለም ሃሳቦች በሙስሊሙ ዓለም ምሁራን ውስጥ እንዲገባ በር ከፍቷል። እንደ አብዱረህማን ጀበርቲ፣ ሸይክ ሐሰን ዐጣር ወ.ዘ.ተ ያሉ የግብጽ ምሁራን ናፓሊዮን ወደ ግብጽ ይዟቸው ከመጡ ምሁራን ጋ

መገናኘት፣ በፈረንሳይ አበረታታችነት አንዳንድ ግብጻውያን ከምዕራቡ ጋር ጎን ለጎን የመጓዝ ጉጉታቸውን አነሳሳው። ይህ ነጥብ ለምን ከዑስማንያ አጼ ግዛት ከሁሉም ቀድማ ለመገንጠል ብርታት የሆናትንና መንገዱን ያመቻቸላትን የብሔርተኝነት መንፈስ በዛ ቀድሞ እንደተነሳ ያብራራልናል። ፈረንሳዮች የቱርክ ሙስሊሞችን አጼ ግዛት በግልጽ ከመዋጋታቸው በተጨማሪ፣ እንደ ቻርሌማን ካሉ ግለሰቦች እና ከመስቀለኞቹ የወሰዱት ፀረ እስልምና ህሱም ሃሳብ ጋ ተዳምሮ የዑስማንያን አጼ ግዛት በመበታተን የሙስሊምን አንድነት ለማዳከም በግብጽ የብሔርተኝነትን ስሜት ለመትከል ሲጀምሩ ጊዜም አልፈጀባቸውም። እንግሊዞችም በዐረብ ምድር ተመሳሳይ ነገር ሲሠሩ ነበር።

የግብጾችን ብሔርተኝነት ለመቀስቀስ እና ግብጻውያን ባለፈ ታሪካቸው ኩራት እንዲሰማቸው ናፖሊዬን *Egyptian Foundation* (የግብጻዊነት መሰረት) የሚል ተቋም መሰረተ። ይህ የሳይንስ ሰዎች ስብስብ የግብጽን ጥንታዊ ታሪክና ባህል የማጥናት ዓላማ ቢኖረውም፣ ዕውነታው ግን በግብጾችና ቱርኮች መሃከል ያለውን ልዩነት ያጠበበውን እስላማዊ አንድነት ለማዳከም ግብጻዊነትን ማነሳሳት ያለመ ነበር። በዚህ ተቋም አማካኝነት ነበር እንደ ክሎት፣ ሴሪሲ፣ ሊናንት እና ፋሴት የመሰሉ ታዋቂ የፈረንሳይ ምሁራን ወደ ግብጽ የተላኩት። ዓላማቸው ግብጻውያን ፈረዖናዊ ባህላቸውን መልሰው እንዲያገኙ እና ከፈረንሳይ ባህል ጋ በማስተሳሰር ህይወታቸውን እና ፖሊሲዎቻቸውን እንዲቃኙ ለማገዝ እንደሆነ መገመት ይችላል።

ሲልቨስተር ደሳሲ እና ሌሎች የፈረንሳይ ምሁራን ስለግብጽ ስልጣኔ ሲጽፉ፣ እንደ ጠህታቪ የመሰሉ የግብጽ ብሔርተኞች ስለጥንታዊ ስልጣኔያቸው ታላቅነት እና ባህላዊ ነጻነት የፃፉትን ያካትታላቸው ነበር፤ ለምሳሌ የደሳሲ *Nationality* መፅሐፍ በአብነት ማንሳት ይቻላል።

ሙሐመድ ዓሊ ከዑስማንያ አጼ ግዛት ነጻነቱን እንዲውጅና ለመጀመሪያ ጊዜ የዐረቦች አንድነት ጥያቄን እንዲያነሳ ያደረገው በፈረንሳዮች ተጽዕኖ ሊሆን ይችላል። ምዕራብያውያ ሚሲዩናውያንም እንዲሁ ንቁ ተሳታፊ ነበሩ። ከ1863 እስከ 1879 ከሰባ ሰባት ያላነሱ የፈረንሳይ፣ አሜሪካ፣ ጣሊያን እና ጀርመን ትምህርት ቤቶች በግብጽ ተከፍተዋል።

ከነዚህ የቅኝ ገዢዎች ጥረት በኋላ ምዕራብ ቀመስ ምሁራን የግብጽ ብሄርተኝነትን ሰንደቅ ተቀብለው ማወለብለብ ጀመሩ። የምዕራቡን ዓለም ስልጣኔ መከተል ሙጥኝ አሉ። ዲፍዓት ጠህታቪ ከነዚህ ሰዎች መሃከል ቀዳሚው ነበር። በፈረንሳይ ለአምስት ዓመታት በቆየባቸው ጊዜያት የሃሳቦቻቸው ተከታይ ሆኖ ተመልሷል። እንደተመለሰም የሞንቲስኮን ስለህዝብ እና አገር ያለውን ሃሳብ አስተጋብቷል።

ጠህታቪ ታዋቂ በሆነው መጽሐፉ *መንሐጅ* ከዚያ ቀደም በግብጻውያን ዘንድ የማይታወቁ “እናት አገር” እና “አርበኝነት” የሚባሉ ቃላትን በምዕራብያውን የብሔርተኝነት ቅኝት ለመጀመሪያ ጊዜ አስተዋውቋል፡ ፡ ግብፃውያን ከሌሎች ሙስሊሞች የተለዩ ሲሆኑ፣ የፍቅራቸውና

ታማኝነታቸው ማዕከል እናት አገራቸው መሆን እንዳለበት አውጇል፡፡ እስልምና ለብሔርተኝነት የማይመጥን አስተሳሰብ ነው ብሎ ተከራክሯል፡፡ ለግብጽ መውደቅ ተጠያቂዎች ግብጻዊ ያልሆኑ ሙስሊም መምሉኮች ናቸው ብሎ፣ ምንም እፍረት ሳይሰማው ፈረንሳይን እና ምዕራብያውን የሳይንስ ስልጣኔ እና ባህል ወካይ ናቸው ሲል ጽፏል፡፡ ግብጻውያን ምዕራቡን መከተል አለባችሁ ሲል መክሯል፡፡

ሌላው ቀንደኛ ብሔርተኛ ያዕቆብ ዞዌ ነበር፤ ከአይሁድ አባት እና ጣሊያናዊ እናት የተወለደ ሲሆን በፈረንሳይ ለበርካታ ዓመታት ኖሯል፡፡ የፈረንሳይ ሰላይም ነበር፡፡ ብሔርተኝነት ለማስፋፋት በፈረንሳይ ኤል ቨታን ኤል መስሪ "የግብጽ እናት አገር" የሚል መጽሔት ያሳትም ነበር፡፡ ከግብጽ ብሔርተኝነት መስራች አንዱ ሲሆን በግብጽ የእንግሊዝ ሃገረ-ገዥ ከነበረው ክሮመር ጋ ጥብቅ ጓደኛ ነበር፡፡

ጣሃ ሁሴይን ሌላው የምዕራቡ ትምህርት ቀመስ ብሔርተኛ ነበር፡፡ አል ሙስተቅቢል አል-ሰቀፍ በሚለው መጽሐፉ ግብጽ ከእስልምና ዓለም ጋ ሳይሆን ከአውሮፓ ጋ የጠበቀ ትስስር እንዳላት ለማሳመን ጥሯል፡፡ በጠሃ ጊዜ በዋፍድ ፓርቲ የተሰባሰቡት ብሔርተኞች በግብጽ ፓለቲካ ውስጥ ቁልፍ ሚና ነበራቸው፡፡ የፓርቲው መሪ የነበረው ሰዓድ ዛግሉል እና ሌሎች ብሔርተኛ ፓለቲከኞች የአውሮፓን ስልጣኔና ዕሴት በግብጽ ዕውን ለማድረግ ብቸኛው መንገድ ነጻነት

ነው ብለው ያምኑ ነበር፡፡ ምዕራብያውን በግብጽ የብሔርተኝነት ዘር የተከሉትና ያፋፉት በዚህ መልኩ ነበር፡፡

### *የቱርክ ብሔርተኝነት*

ብሔርተኝነት ወደ እስልምና ዓለም ከገባባቸው ቀደምት በሮች መሃከል ቱርክ ሌላዋ ቀዳማይ ምድር ነች፡፡ በርራንድ ሊዊስ እንደተናዘዘው በቱርክ ብሔርተኝነት መንፈስ ያነሳሱት ሶስት አይሁዶች ነበሩ፡፡

በቱርክ የመጀመሪያው የብሔርተኝነት እሳት ለመጫር ሲታትር የነበረው አርተር ሉምሌይ ዴቪድ ይባል ነበር፡፡ እንግሊዛዊ አይሁድ ሲሆን ወደ ቱርክ ተጉዞ *ቀዳሚዎቹ ትርክቶችን* (Premilinary Discources) ፅፏል፡፡ በመጽሐፉ ስለቱርኮች ልዩ ዘርነት፣ በዐረቦች እና ሌሎች የምስራቅ ዘሮች ስላላቸው የበላይነት አትቷል፡፡

ሊውስ እንደጻፈው “የዚህ እንግሊዛዊ አይሁድ መጽሐፍ ቱርኮችን የተለዩ እና ነጻ ህዝብ እንደሆኑ እንዲያስቡ አድርጓቸዋል፡፡” የምዕራብያውኑ ሃሳቦች ከመግባታቸው በፊት በዑስማንያ አጼ ግዛት ምንም አይነት የብሔርተኝነት ምልክት አይታይም ነበር፡፡ እስከ 20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን መጀመሪያ ድረስ ቱርኮች ዐረቦችን እንደልዩ ዜጎች አያይዋቸውም፡፡ ዐረቦችም በዑስማንያ አጼ ግዛት ውስጥ መካተታቸው አልጎረበጣቸውም፡፡ ቱርኮችም ዐረቦችን በባህላቸውና በቋንቋቸው አክብረዋቸው ኖረዋል፡፡ የሱልጣን

አብዱልሐሚድ የቅርብ አማካሪዎቹ ዐረቦች ነበሩ። ከነርሱ ውስጥ ዐቦል ሆዳ እና ዒዛ ፓሻ ይታወቃሉ። በ1908 በአብዲልሐሚድ ላይ በተነሳው አብዮት፣ አብዮቱን ከመሩት መሪዎች መሃከል ሁለቱ- ዐዚዝ ዓሊ መስሪ እና ማህመድ ሸውካት ፓሻ ዐረቦች ነበሩ። ነገር ግን የተጠቀሰው የአይሁድ መፅሐፍ የYoung Turks ቅስቃሴ መሪዎችን ልብ ማሸፈት ችሎ ነበር።

በ1851 ፉዓድ እና ጀውዳት ፓሻ የዴቪድን በርካታ ጽሑፎች ወደ ቱርክኛ መልሰውታል። በ1869 ዓሊ ሳቪ የሚባል ሌላ ቱርካዊ ስለቀደምት ቱርክ ዘር ታላቅነት በቱርክኛ ጽፏል። የዴቪድ ስራ ግልባጭ ነበር። ይህ ብሔርተኝነት የተንጸባረቀበት በቱርካውያን ከተጻፉ መጽሐፍቶች መሃከል የመጀመሪያው ሲሆን በዑስማንያ አዔ ግዛት ውስጥ ፈጽሞ ያልተጠበቀ ነበር። “እናም ቱርኮች በምዕራብያውያን አጋዥነት ብሔርተኝነታቸው አገኙ፤ የምዕራብውያንን ጽሑፎች ገለበጡ ብሏል ሊዊስ።

የቱርክን ብሔርተኝነት ለማስፋፋት ከፍተኛ አስተዋጽኦ ያደረገው ሌላው ፀሐፊ ፈረንሳዊው አይሁድ ዴቪድ ሊዮን ኮኸን ነበር። በ1899 *Introduction Generale a l`Histoire de L’Asie* ተብሎ በተሰየመው መጽሐፉ ስለቱርክ ዘር የበላይነት እና ጥንታዊ የገድል ታሪኮቻቸውን ጽፏል። መጽሐፉ በ20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የመጀመሪያዎቹ አስሮች ዓመታት ውስጥ ወደ ቱርክኛ ተተርጉሞ በብዛት ተሰራጭቷል። እንደ ኘሮ ኻዱሪ እና በርናንድ ሊዊስ

የYoung Turks አቀንቃኞች ስለ ፓን-ቱርክ እንዲያስቡ ያነቃቃቸው ይህ መጽሐፍ ነበር።

ከዚህ መጽሐፍ በተጨማሪ ኮኸን ስለቱርኮች ጥንታዊ ታሪክ ልዕልና የሚተርኩ በርካታ ታሪኮችን አከታትሎ ጽፏል። የዚህ አይሁድ ፀሐፊ ዓላማ የቱርኮችን የዘር የበላይነት ቅይድ ሃሳብ (prejudice) ማገንገን እና ከሌሎች የሙስሊም ህዝቦች ጋ ያላቸውን አንድነት ማዳከም ነበር። ይህ ሰው በጽሑፍ ብቻ አልተወሰነም። በፓሪስ የተሳደዱ የቱርክ እና ግብጽ ህብረተሰብ የሚል ስብስብ ፈጥሮ በየሃገሪቱ የብሔርተኝነት ቅስቃሴ መሰረት ጥሏል።

የቱርኮችን እና ዐረቦችን ብሔርተኝነት በመፍጠር ታላቁን ሚና የተጫወተው ታዋቂው ምስራቃዊው አርሚነስ ቫምቤሪ ነበር። የሃንጋሪ አይሁድ ቄስ ሲሆን የቱርክ ብሔርተኝነት፣ ቋንቋ እና ስነ ጽሑፍ መነቃቃት ግዴታ እንደሆነ በበርካታ ስራዎቹ ጎትጉቷል። ሥራዎቹ ምዕራብ ቀምስ የተበራዩ የሚባሉትን የቱርክ ምሁራንን ቀልብ ክፉኛ የሳበ በመሆኑ በውስጣቸው የአርበኝነት ስሜትን ቆስቁሷል። ሰውየው ከቱርካውያን የመንግስት ሰዎችና ፓለቲከኖች የቅርብ ግንኙነት ነበረው።

አይሁዶች በሙስሊሞች ውስጥ የብሔርተኝነት ስሜትን ካቀጣጠሉበት ዋነኛ ምክንያት መሃከል አንዱ የፍልስጤምን ምድር ለመያዝ መንገድ መጥረጊያ ስለሆነ ነበር። በፍልስጤም ምድር የአይሁዶችን መንግስት ለመመስረት ከሱልጣን አብዱልሐሚድ ጋ ተከታታይ ያልተሳኩ ሙከራዎችን ማድረጋቸው፣ ህልማችውን

ለማሳካት ሱልጣን አብዱልሐሚድን ከስልጣን ማውረድ፣ እስልምናን መሰባበር እና በቱርኮችና ዐረቦች መሃከል ያለውን አንድነት መከፋፈል ብቸኛው መንገድ እንደሆነ ወስነዋል። በብሔርተኝነት ስር የYoung Turks ምስረታን በመጠንሰስ ፅዮናውያኑ አብዱልሐሚድን ከስልጣን ማውረድ ችለዋል። ከዛም በቱርኮችና ዐረቦች መሃከል ልዩነት በመፍጠር የጥላቻን ዘር ዘርተዋል።

Young Turks የተባለው ስብስብ ፖሊሲዎቻቸውን በቱርኮች የበላይነት እምነት ላይ ቀረጹ። ፀረ-ዐረብ አቋምም ያዙ፤ የዐረብ ባህል ማዕከላትን እና መሰብሰቢያዎችን ዘጉ፤ በዐረቦች እና ቱርክ ባልሆኑ ዜጎች ላይ አድሏዊ ተግባር መፈፀም ወዲያውኑ ጀመሩ። ይህ ደግሞ እንግሊዝ ለዐረብ ብሔርተኝነት ከጠነሰሰችው ሴራ ጋ መሳ ለመሳ ሄደ።

ፅዮናውያኖቹ እና ኢምፔሪያሊስቶቹ በአንድ በኩል ዐረቦችን ያገላሉ፤ በሌላ በኩል የዐረብ ብሔርተኝነትን እና በቱርክ ላይ ጠላትነትን ያቀጣጥላሉ። እስከዚያ ጊዜ ድረስ ዐረቦች ራሳቸውን እንደተለዩ ዘሮች አይቆጥሩም ነበር። ነገር ግን ቱርኮች የቱርክ ባህልን በሌሎች ላይ በበላይነት ሲያራምዱ፣ ዐረቦችም የራሳቸውን ነጻ ማንነት ለመያዝ መሞከራቸው ተፈጥሮዋዊ ነገር ነው። የYoung Turks ዘረኛ እና ብሔርተኛ ፓሊሲዎች ነበሩ የዐረቦችን የብሔርተኝነት እሳት ያቀጣጠሉት።

ከ1908ቱ አብዮት በኋላ Young Turks የቱርክን ብሔርተኝነት በጉልበት እና በመገናኛ ብዙሃን ኘሮፓጋንዳ ማስፋፋትና ማጠናከር

ጀመሩ፡፡ በተጨማሪም የዐረብ ብሔርተኞች ቱርኮች ላይ እያሳረፉ በነበሩት ተደጋጋሚ ቡጢዎች፣ ከአውሮፓ በመጡ ተማሪዎች የቱርካውያኑ ብሔርተኝነት ጦዘ፡፡ ናመክ ከማል፣ ዚያ ፓሻ እና ጀውዳት ፓካ የመሳሰሉ ሙስሊም አብሰልሳዬች እስልምናን እና ብሔርተኝነትን ለማጣጣም ሙከራ አድርገው ነበር፡፡ የብሔርተኝነት ጉዞ እና ቅኝ ግዛት ተዳምረው አታ ቱርክን ከፀረ እስልምና ፓሊሲው ጋ አስነሳው፡፡

## *የእንግሊዝ ቅኝ ግዛት፡ የዐረብ ብሔርተኝነት ፊት አውራሪ*

የምዕራብያውያኑ ሃሳብ እና ቅኝ ግዛት ተጽዕኖ ከመግባቱ በፊት ብሔርተኝነት በዐረብ ምድር አይታወቅም ነበር፡፡

ከ16ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ጀምሮ የመካከለኛው ምስራቅ ምድር በሙሉ በዑስማንያ አጼ ግዛት ስር ነበር፡፡ እስከ 20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን መጀመሪያ ዐረቦች ከቱርኮች የተለዩ እንደሆኑ ተሰምቷቸው አያውቅም፡፡ በተጨማሪም ቱርኮቹም በዐረቦች ላይ ልዩነት አድርገው አያውቁም፡፡ የዐረቦችን ምድር ለአስተዳደር ምቹነት በተለያዩ ዞኖች ቢከፍሏቸውም፣ ዞኖቹን የሚያስተዳድሯቸው ራሳቸው ዐረቦቹ ነበሩ፡፡

በግብጽ የፈረንሳይ ቅኝ ገዥዎች ብሔርተኝነትን እና መገንጠልን ሲያስፋፉ፣ በቱርክ ፅዮናውያን እና ኢምፔሪያሊስቶቹ Young Turks ፈጥረው የቱርካዊነትን የበላይነት እየመሰረቱ ዐረቦችን ሲያገሉ፣

እንግሊዝ በበኩሏ በምሁራኞቿና ሚስዮናዊያኖቿ በዐረቦች ውስጥ የብሔርተኝነት እና ዘረኝነት ስሜት እየጋገረች ነበር፡፡

ከግብጽ ቀጥሎ የዐረብ ብሔርተኝነትን ቀንዲል የተቀበሉት ሶሪያ፣ ሊባኖስ እና ዮርዳኖስ ነበሩ፡፡ በነዚህ ክልሎች ሚስዮናውያን እጅግ ንቁ እንቅስቃሴ ያደርጉ ነበር፡፡ ከ1830 ጀምሮ የካቶሊክ ኢየሱሳውያን አባላት፣ ከ1820 ጀምሮ ደግሞ ኘሮቴስታንቶች በሶሪያ ገብተዋል፡፡ ሰፊው የክርስትና ማህበረሰብ የቅኝ ገዥዎችን ሴራ በመተግበር ተሳታፊ ሆኑ፡፡ ክርስትያን ዐረቦች የምዕራብያውያኑን መግባት እንደጥቅም ነበር የተመለከቱት፡፡ የእንግሊዝ እና ፈረንሳይ ቅኝ ገዢዎች እንደሚያዳክሙላቸው ተመልክተዋል፡፡ የምዕራብያውያን ትምህርት በመማር ረገድ ከሙስሊሞች የቀደሙ በመሆናቸው በቅኝ ገዥ ሃይሎች እንታመናለን፣ የማስተዳደሩም ጉዳይ ለኛ ይሰጠናል ብለው አስበዋል፡፡ ክርስትያን ዐረቦች ከሙስሊም ዐረቦች ጋ በነበራቸው ስጥ አገባ የአውሮፓውያንን ዕርዳታ ሲፈልጉም ነበር፣ በ1860 እንደታየው፡፡ ሆኖም ይህ አካሄድ ችግሮቻቸውን አልፈታውም፤ የሙስሊሞችን ጥላቻ ቀሰቀሰባቸው እንጂ፡፡ እናም ብርሔተኝነትን እንደ አማራጭ ተቀብለው ወደ ዐረቦች እምበርት አደረሱት፡፡

በዚህ በኩል ዋናው ሰው የዐረብ ብሔርተኝነት መስራቹ ነጂብ አዚሪ ነበር፣ የፈረንሳይና የእንግሊዝ ሰላይ ነበር፡፡ በ1904 Le Reveil de la Nation Arabe የሚል መጽሐፍ በፈረንሳይ አሳትሟል፡፡ Ligue de la Patrie Arabe የሚል ስብስብም መስርቷል፡፡ L’

Independence Arabe የሚባል ወርሃዊ ጆርናልም ያሳትም ነበር። በህትመት ስራው ከፈረንሳይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ባልደረባ ኡገን ለንግ ጋ በቅርበት ሰርተዋል። ለንግ እንደ ፈረንሳይ ቅኝ ገዥ አገልጋይነቱ La Revolte Arabe የተሰኘ ስለዐረብ ዘር የበላይነት የሚናገር መጽሐፍ ጽፏል። በዚህ መጽሐፍ ውስጥ በተደጋጋሚ ሲነሱ ከነበሩት ነጥቦች መሃከል በዐረቦችና ቱርኮች መሃከል ስላለው የዘር፣ የባህል እና የፖለቲካ ልዩነት ሲሆን፤ አሁንም አሁንም ዐረቦች በቱርኮች ላይ ስላላቸው የበላይነት እና በቱርክና በዐረቦች መካከል ልዩነት ስለመኖሩ አስፈላጊነት አንስቷል። ለአዚሪና ለንግ የቱርኮችን አጼ ግዛት ለማንኮታኮት ሶስት አብዮቶች ያስፈልጉት ነበር፡ የዐረቦች አብዮት፣ የኩርዶች አብዮት እና የአርመኖች አብዮት።

አዚሪ በዓለም አቀፍ ፖለቲካ ላይ ያለው ዕይታ በእንግሊዝና ፈረንሳይ ላይ ጥገኛ ነበር። በቱርኮች ላይ ለማመጽ የእንግሊዞችን ወዳጅነት፣ አፍቃሪ እንግሊዝ የሆነውን የመሐመድ ዋሂዲ ፓርቲን እና እንደ "አል- ሐግታተም" እና "አል-ወጣን" የመሰሉ አፍቃሪ እንግሊዞችን እርዳታ ጠይቋል። የዑስማንያ አጼ ግዛት ደጋፊ የነበረችውን ጀርመንን ለሰው ዘር አደጋ እንደሆነች ሲቆጥራት፣ የእንግሊዝንና የፈረንሳይ መንግስታትን የዓለም ፍትህ አስፋኝ አድርጎ ሾሞ፣ እነዚህ የቅኝ ገዥ ሃይሎች በቱርክ ጣልቃ እንዲገቡ ወትውቷል። በዑስማንያ አጼ ግዛት ውስጥ ከለንግ ጋ በመተባበር አብዮት ለማስነሳት ፈቃደኛነቱን ሰጥቷል።

ዶ/ር ሐሚድ ኤንያት ሲጽፍ “አዚሪ ለእንግሊዝና ፈረንሳይ ያለውን ታማኝነትና ታዛዥነት የገለፀ ሲሆን፣ ራሱንም በምስራቁ ዓለም የጥቅማቸው ደጋፊ አድርጎ ‹ፈረንሳዮች ሊረዱን ከኛ ምን እንደሚፈልጉ ሊነግሩን ይገባል› በማለት አስተዋውቋል።”

ከአዚሪ በተጨማሪ እንደ ጴጥሮስ ቦስታኒ፣ ናሲፍ አል-ያጂዚ፣ ኢብራሒም አል-ያጂዚ፣ ኖፍል፣ ሌሊም ኖፍል፣ ሚካኤል ሻምሃዳ፣ ሰምዓን ካልሁን፣ ገርጅስ ፈያዝ፣ ራስታን ዳመሽግያ እና ሌሎች በርካታ ክርስትያን ምሁራን የዐረብ ብሔርተኝነትን ለመቀስቀስና ለማስፋፋት ከቅኝ ገዥ ሃይሎች ጋ ተባብረዋል። እነዚህ ሰዎች ዐረቦች የመጠቁ ዘሮች እና ከሌሎች ሙስሊሞች የተሻሉ እንደሆኑ ለማሳመን ክፉኛ ደክመዋል። ለዚህ ዓላማቸው መሳካት ታሪክን አጣመዋል፤ እስልምና፣ እስላማዊ ባህል እና ስልጣኔ በዋናነት ዐረባዊ እንደሆነ አቅርበዋል። መከራካሪያቸውን እና መንገዳቸውን ያገኙት ከምዕራቡ ባህል እና አስተሳሰብ ነበር።

የዐረብ ብሔርተኝነት የተንጸባረቀው በሁለት መንገዶች ነበር፡ በግብጽ፣ ሶሪያ፣ ኢራቅና ሌሎች ህዝቦች ላይ በማተኮር እና ሁለተኛ በዐረቦች አንድትና ዘር ዙሪያ በማጠንጠን።

በአንደኛው የዓለም ጦርነት የእንግሊዝ መንግስት በግልፅ የዐረብ ብሔርተኝነትን በመደገፍና በመከላከል፣ በዐረቦችና በቱርኮች መሃከል ያለውን ጠላትነት ለአገሪቷ ጥቅም ማዋል ጀመረ። የዮርዳኖሱ ንጉስ ሁሴይን አያት የሆኑ ሸሪፍ ሁሴይን በሰኔ 1916 በቱርኮች ላይ መነሳታቸው ተፈላጊው የዐረብ ብሔርተኝነት ውጤት እንደሆነ

ተቆጠረ። የዐረብ ብሔርተኝነት መስፋፋት የእንግሊዝ እና የፈረንሳይ መንግስታትን በአንድነት እንዲሰሩ ጋብዟቸዋል።

የሸሪፍ ሁሴይን ከእንግሊዞች ጋ የመተባበርና እንደ የዐረብ ብሔርተኝት ጀግና የመቆጠሩ ታሪክ በራሱ የሚገርም ነው። በ1914 ሸሪፍ ሁሴይን በልጃቸው አብደላህ- የንጉሥ ሁሴይን አባት ነበሩ- አማካኝነት ከታዋቂው የእንግሊዝ ጄኔራል ኪችነር ጋ ይገናኛሉ። ከትንሽ ጊዜ በኋላ ኪችነር ኖናልድ ሶቶርስ የተባለ ከፍተኛ ባለስልጣን አብደላህን እንዲጎበኘው ያደርጋል። በዚህ መሃል የአንደኛው የዓለም ጦርነት ይቀሰቀሳል። በጥቅምት 1914 የእንግሊዝ የጦር ዋና ፀሐፊ የሆነው ክሪችነር ነጻነታቸውን እንዲቀዳጁ በቱርኮች ላይ እንዲያምፁ መልዕክት ይሰዳል። ክሪችነር ዐረቦች ለነጻነታቸው የሚያደርጉትን ትግል እንደሚያግዝና ኸሊፋነቱን ከቱርኮች ወደ ዐረቦች እንደሚያዞር እና ሸሪፍን አዲሱ ኻሊፍ እንደሚያደርገው ሁሉ ቃል ይገባል።

ሸሪፍ ሁሴይን ቱርክ በእንግሊዞችና በፈረንሳዮች ቁም ስቅሏን እያየች ባለችበት ወቅት ዐረብ ሙስሊሞች በነጻነት ስም ቱርኮች ላይ በማስነሳት የእንግሊዞችን የቅኝ ግዛት ዕቅድ አሳለጠ። የእንግሊዙ ጄነራል ማክማሆም ለሸሪፍ ሁሴይን “የዐረብ ህዝብ ለነጻነቱ በሚያደርገው ትግል” ወሳኝ ሃይል ሲል የአድናቆት መልዕክት ላከለት። የደብዳቤው ኮፒ አሁንም በእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ቢሮ መዝገብ ቤት ውስጥ ይገኛል።

በሐምሌ 21/1915 ሸሪፍ ወደ ማክማሆም የኸሊፋነት ፍላጎቱን እንድታሳካለት እንግሊዝ እንድትረዳው የሚጠይቅ ደብዳቤ ላከ። በሰኔ

10/1916 በእንግሊዝ ጦር እና የፓለቲካ ድጋፍ የሚደረግለት የዐረቦች አመጽ በሸሪፍ ሁሴይን ተጀመረ። ቲ.ኢ.ለውረንስ የእንግሊዝ የመንግስት ባለስልጣን ሲሆን በዓመፁ ለሸሪፍ ልጅ ለፈይሰል ዋና አማካሪ ነበር። በአንድ በኩል የዐረቦች ሃይል ቱርኮች ላይ ሲነሳ፣ እጅግ በተቀናጀ መልኩ የእንግሊዙ ኮማንደር ጀነራል አለን ቢ በፍልስጤም ውጊያ ሲያደርግ ነበር። የዐረቦች የነጻነት ትግል የተቀሰቀሰው በብሔርተኝነት ሲሆን በእንግሊዝ ጦር እንክብካቤ ተደርጎለታል።

የእንግሊዞችና የፈረንሳዮች ቅኝ ገዥ ሃይሎች ዐረቦች ለነጻነታቸው ትግል እንዲያደርጉ ሲጎተጉቱ፣ ሸሪፍ ሁሴይን እና እንደ አል-ፈታህ እና አል-አሃድ የመሰሉ ምስጢራዊ ድርጅቶች በንቃት የቅኝ ገዥዎቻችን ዕቅድ ሲያስፈጽሙ፣ እንግሊዝና ፈረንሳይ በምስጢር የዐረቦችን ክልል ለመከፋፈል በምስጢር እየሰሩ ነበር። በSykes-Picot እና በBalfour Declaration ስምምነቶች የዐረብ ምድርን ክፍፍል እና የጽዮናዊት አገርን ምስረታ መንገድ ጠረጉ።

ፈረንሳይ ፀረ ቱርክ ስሜትን በማነቃቃት አልጄሪያ፣ ቱኒዝያንና ሞሮኮን ስትይዝ፣ ጣሊያን ሊቢያን ተቆጣጠረች። ራሽያ የተወሰኑ የአርመንያን ክፍል የድርሻዋን ስትወስድ፤ እንግሊዝ ግብጽን፣ ሳይፕረስን፣ ኤደንን፣ የፐርሽያ ባህረ ሰላጤ ግዛት ሸኮችን እና ሶሪያ፣ ሊባኖስ እና ኢራቅን ዋጠች። የዐረብ ብሔርተኝነት አሳዛኝ ታሪክ ይህን ይመስላል።

* * *

ብሔርኝነት ወደ እስልምና ዓለም የገባው በምዕራብያውያኑ እንደሆነ ግልጽ ነው፡፡ የእንግሊዝ እና የፈረንሳይ ሚሶናውያን እና ምስራቅያውያን የአንበሳውን ድርሻ ይወስዳሉ፡፡ ቅኝ ገዥ ሃይሎች ሲስፋፉት እስላማዊውን አንድነት ለመሰባበርና የዑስማንያ ዐዔ ግዛት ለማጥፋት አገልግሎት ላይ ውሏል፡፡ ከዚሁ ጋ በተያያዘ የክርስቲያንና አይሁድ ህዳጥያን እና የምዕራብያውያን ትምህርት ቀመስ ሙስሊሞች የኢምፔሪያሊዝምን ዕቅድ በማሳካት ዋናውን ሚና ተጫውተዋል፡፡ ሁሉም ማለት በሚያስችል ደረጃ በኢስላማዊው ምድር የብሔርተኝነት ቀንዲል የተሸከሙ፣ ይህን የምዕራብያውያን ዕሴትና ዕሳቤ የያዙት ነበሩ፡፡

የምዕራብ ዕሳቤዎች የሙስሊሙን የአስተሳሰብ መንዱን ሲይዙ "እናት አገር" እና "አርበኝነት" የመሰሉ ቃላት በዐረቦች፣ ቱርኮች እና ኢራኖች ዘንድ ታዋቂ ሆኑ፡፡ ብሔርተኝነት የሙስሊሙን ዓለም እስላማዊ አንድነት ለመበጣጠስ በቅኝ ገዥ ሃይሎች የሰረገ የምዕራቡን ዓለም ተምሳሌት ለመከተል የሚደረግ ትግል ነው፡፡ በግብፆች ሆነ በሌሎች ሙስሊም ህዝቦች ውስጥ ብሔርተኝነትን ለማስረጽና ለማስፋፋት ከቃላት ባሻገር በተግባር በንቃት የተሳተፉት እንግሊዝና ፈረንሳይ መኖራቸው ይህ አብነቱ ነው፡፡

እዚህ ላይ ሊነሳ የሚችለው አስፈላጊ ጥያቄ፣ በቅኝ ገዥ ሃይሎች እና የምዕራብ ትምህርት ቀመስ ሃይሎች ወደ እስላማዊው ዓለም የገባው ብሔርተኝነት ቀላል ቁጥር በሌለው ህዝብ ተቀባይነት እንዴት ሊያገኝ ቻለ? የሚለው ይሆናል፡፡

መጀመሪያ ሠፌው ህዝብ በ"አርበኝነት" እና "ብሔርተኝነት" በሚባሉት ጽንሰ ሀሳቦች መሃከል አስፈላጊውን ልዩነት ማበጀት አልቻለም፡፡ ሁለቱን ቃላት አንድ አድርጎ መቁጠር ብቻ አይደለም፤ ዑምማ ከሚለው የእስልምና ፅንሰ ሃሳብ ጋር አዳብሎታል፡፡ እስልምና ከጅምሩ ስለዑምማ ጠንካራ አቋም ነበረውና ሠፌው ህዝብ ብሔርተኝነትን ከዑምማ ጋ አንድ ነው ብሎ አምኗል፡፡

ሁለተኛ፤ ከቀንደኞቹ የብሔርተኝነት አቀንቃኞች በተቃራኒ ሠፌው ህዝብ የብሔርተኝነት ስሜትን የተጠቀመበት በእግሊዞችና ፈረንሳዮች የተጫነበትን ማህበራዊ በደል ለመቃወም ነበር፡፡ ለህዝቡ ብሔርተኝነት የአስተሳሰብ ትምህርት ቤት ሳይሆን ስሜት ሲሆን፤ ለተማሩት መደብ እና ፓለቲከኞች ብሔርተኝነት ርዕዮተ ዓለም እና የፓለቲካ ዐቂዳ ነበር፡፡ በሠፌው ህዝብ ብሔርተኝነት ሊስፋፋበት የቻለው ሶስተኛው ምክንያት በሐሳዊ ሙስሊም ባለስልጣናት የሚደርስበት በደል እና ጭቆና መማረሩ ነበር፡፡

የዑስማንያ አጼ ግዛት መውደቂያው ሲቃረብ በታሪክ እንደታዩት እንደማንኛው ራስ ወዳድ መሪዎች በዐረቦች ብቻ ሳይሆን በቱርካውያን ገበሬዎች ላይ በደላቸው ከፍተኛ ደረጃ ደርሶ ነበር፡፡ የቱርክ ብሔርተኝነት ውጤት የሆኑት Young Turks ስልጣን ላይ ከወጡ በኋላ ደግሞ በዐረቦች ላይ ያረሱት በደል ከፍተኛ ደረጃ ላይ በመድረሱ በዐረቦች መሃከል የብሔርተኝነት ስሜት ተስፋፋ፡፡ ቅኝ ገዥዎችም ይህን ክፍፍል በአግባቡ ተጠቅመውበታል፡፡ በዚህ ረገድ የቅርብ ጊዜ ታሪክ እንደ አብነት ካነሳን የባንግላዴሽ ምስረታ ነው፤

**በፓኪስታን ጦረኛ አምባገነኖች ምክንያት ባንግላዴሽ ልትፈጠር ችላለች።**

## ምዕራፍ ሶስት፡ የብሔርተኝነት ምንነት

### *የብሔርተኝነት ብያኔ*

የፓለቲካ ሳይንስ ምሁራን ለብሔርተኝነት የተለያዩ ብያኔዎችን ሰጥተዋል፡፡ ካርልተን ሄይስ (Carlton Hayes) "ህዝብ ማለት የጋራ ንፅርያተ-ዓለም እና የባህል ትውፊት ያለው ነጻ የፓለቲካ ስብስብ ነው፡፡" በዚህ ብያኔ መሠረት የጋራ የፓለቲካ ስብስብ እና የባህል አንድነት ህዝብን ለመፍጠር ዋና መሠረቶች ናቸው፡፡

እንደ ሃንስ ኮህን (Hans Kohn) ገለጻ ደግሞ "የአንድ ስብስብ በአንድ ግዛት ውስጥ መኖር ህዝብ ለመፍጠር ብቸኛው ግብዓት ነው፡፡ በተፈጥሮዊ እና ክልላዊ ከባቢ ውስጥ ማደግ በግለሰቦች መሃከል ወንድማማችነትን ይፈጥራል፡፡ በዚህ መሠረት ላይ የቆመ ስብስብ የጋራ ፍላጎት እና ምቹ ሁኔታ ስሜት እንዲዳብር ስለሚያደርግ ህዝብ ይፈጥራል፡፡"

ሊውጎ (Luigo) እንዲሁ "ህዝብ ማለት በክልል፣ ደም፣ ቋንቋ እና ባህል ወይም ታሪክ የተሳሰሩ ግለሰቦች ስብስብ ነው" ብሏል፡፡

ሳሎ ባረን (Salo Baron) ሲያብራራ "ህዝብ የሚለው ቃል ጥቅም ላይ የሚውለው በተመሳሳይ መሬት እና በጋራ የፓለቲካ ተቋማት ለተሳሰሩ የሰዎች ስብስብ ነው" ብሏል፡፡

ኮህን ስለ፤ ብሔርተኝነት ፀባይ የሚከተለውን ብሏል። "ለእናት አገር ጥልቅ የትስስር ስሜትና ፍጹም ታማኝነት፣ እንዲሁም ዕጣ ፈንታዋን የመጋራት መንፈስ መላበስ የብሔርተኝነት መሠረት ናቸው። ለሌሎች ያለን ታማኝነት ለእናት አገር ካለን ታማኝነት የበታች ካልሆነ ትክክለኛ ሊሆን አይችልም።"

የአሜሪካን ኢንሳይክሎፒዲያ (ባህረ ሃሳብ) ብሔርተኝነት በሚከተለው መልኩ በይኖታል፡ በብሔርተኝነት ጥያቄ ላይ ለብሔራዊ አንድነት ታማኝነት እና ትስስር ከየትኛውም ዐይነት ትስስር የበለጠ ዋጋ አላቸው፤ ለህዝብ ስኬት ኩራት መሰማት፣ በራስ ህዝብ ልዩ-ነት እና ከሌሎች ህዝቦች የበላይ ነን የሚል ጥልቅ እምነት መኖር ሌሎች የብሔርተኝነት መለያዎች ናቸው።

ሄይስም ይህን ሃሳብ በመደገም ጽፏል። "ለስብስቡ ንዑስ ምንነት (ህዝብና መሬት) ታማኝነት እና ትስስር መኖር የብሔርተኝነት መሰረት ናቸው።"

እነዚህ ብያኔዎች ሁለት ነጥቦችን ግልጽ ያደርጉልናል። 1. ለክልል፣ ደም ወይም ቋንቋ እውነተኛ መስጠት የብሔርተኝነት መሰረት ነው። ብሔርተኝት መሰረቱን የጣለው በቋንቋ፣ ክልል እና ዘር ላይ ነው። እናት አገር እና የብሔር አባልነት የአርበኝነት ማጠንጠኛ ናቸው። ማንነትን በመበየን ረገድ የብሔርተኝነት ት/ቤት የሚከተለውን ይላል፡
:

*በሰዎች መሃከል ልዩነት የሚፈጥረው የትውልድ ቦታ፣ አገር፣ ቋንቋ እና ዘር ናቸው። በእናት አገር እና ህዝብ ቤት ውስጥ ያሉት የራስ ወገን ሲሆኑ፣ ከቤቱ ግድግዳ ውጭ ያሉት እንግዳ ፍጡር ናቸው። የህዝብ ጥቅምና ምቾት የግለሰቦችን ወይም ስብስቦችን ባህሪይና ተግባር ትክክለኛነት እና ስህተት፣ ጥሩነት እና መጥፎነት እና የሁሉ ነገር መመዘኛ ናቸው።*

ለብሔርተኝነት ት/ቤት ከህዝቦች ምስረታ ጀርባ ያሉት ግብዓቶች በምንነታቸው ቁሳዊ ናቸው። እንደ ክልላዊ ድንበር፣ ዘር እና ፓለቲካዊ አቋም። በነዚህ ነገሮች መሰረት ላይ ነው ህዝቦች የጋራ ዕጣ ፈንታ እና ያለፈ ታሪክ የሚኖራቸው።

2. ሌላው የብሔርተኛ መሰረታዊ መለያ ለእናት አገር ያለ ፍጹም ታማኝነት ነው። ለሌሎች ያለ ታማኝነት- ለአምላክ፣ ለሃይማኖት፣ ለበጎ ነገሮች ወ.ዘ.ተ የሚኖር ታማኝነት- ለአገር እና ህዝብ ባለ ታማኝነት ላይ ጥገኛ ናቸው። የትኛውም አይነት ታማኝነት አርበኝነትን መቆጣጠር የለበትም። ሃይማኖት ወይም ምክንያታዊነት ከአርበኝነት ጋ ከተጋጨ አርበኝነት ትክክል ነው።

የትኛውም ብሔርተኛ ሊዘነጋቸው የማይገቡ መሰረታዊ መርሆዎች እነዚህ ናቸው። ሰው መኖር ያለበት ለአገሩ ነው፤ ከእናት አገሩ ውጭ ለምንም ነገር ሕይወቱን መስጠት የለበትም። ለግለሰብ ሆነ ማህበረሰባዊ አቋም አቅጣጫ የሚሰጠው ከአምላክም፣ ከሃይማኖትም ጋ ያለ ቁርኝት ሳይሆን ከብሔርተኝነት ጋ ያለ ቁርኝት ብቻ ነው።

የሰው ልጅ የኩራት ምንጩ የሁለንተናዊ ዕሴቱ ዕድገት ታሪክ ሳይሆን ብሔራዊ ታሪኩ ነው፡፡

አንድ ብሔርተኛ ህዝብ እና አገር ከሌሎች ምንነቶችን ሁሉ የበላይ ሲሆን መልካም ነገሮች ሁሉ መሠራት ያለባቸው ለሁለቱ ነው፡፡

## ሌሎች የብሔርተኝነት መለያዎች

ለብሔርተኝነት፣ የግለሰብን እና የማህበራዊ ህይወትን የሚመራው ምሁራዊ እና ፓለቲካዊ ቁመናን የሚበይነው ጠንካሮቹ ነገሮች አገር/ክልል እና ህዝብ እንደሆኑ ደጋግመን አይተናል፡፡ ኢብን ኸልዱን እንዳለው ከብሔርተኝነት ጀርባ ያለው አላባ አርበኝነት ነው፡፡ ከሌሎች የብሔርተኝነት መለያዎች መሃከል የተወሰኑት

1. የኔ የምንለውን ወገን ከውጭ አካል መከላከል፤ የውጭው አካል ትክክል ሆነ አልሆነ፡፡
2. የአገሪቱን ታሪካዊ እና ብሔራዊ ሰብእናዎችን እስከማምለክ በሚደርስ ደረጃ ማውሳት፡፡
3. ያለፈ ልምድን፣ ጥንታዊ ጣዖት አምልኮ ቢሆኑ እንኳ መቀስቀስ፡፡ በዚህ ረገድ ድህረ-ብሔርተኞች በወጎች፣ በጥንትና የሞቱ ልምዶች ላይ ይንጠለጠላሉ፡፡

የግብጽ ብሔርተኞች አንደበተ ርቱዕ ቃል አቀባያቸው ጠሃ ሁሴይን የጥንታዊ የፈርዖኖችን ስልጣኔ ቅሪቶችን ህያው ለማድረግ የቻለውን

ሞክሯል፡፡ ሎፍቲ አል ሰይድ ታዋቂ የግብጽ ብሔርተኛ ሲሆን የታሪካቸውን ቀጣይነት ህያው ለማድረግ የአንቀባራዊውን ጥንታዊ የግብጽ ስልጣኔ ዕውቀት ሊኖራቸው ግድ ይላል ሲል መክሯል፡፡ በኢራናዊ ብሔርተኞችም የኢራንን ህዝብ ከነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) እና ቤተሰቦቻቸው ጋ ሳይሆን ከሳይረስ እና ዳርየስ ጋ ለማቆራኘት ጥረዋል፡፡

4. አገርን/ክልልን ለማላቅ ታሪክ ማዛባት፣ ታሪክ መፍጠር
5. ልክ እንደ ጥንታዊው ቶተሚዝም በብሔርተኝነት ውስጥ የቅድስና ክብር የተሰጣቸው ልዩ ተምሳሌቶች አሉ፡፡ ባንዲራ፣ ብሔራዊ አርማ እና የህዝብ መዝሙር እንደ ቅዱስ ይወሰዳሉ፡፡ ለእነዚህ ሲል እያንዳንዱ ሰው ራሱን መስዋዕት የማድረግ ግዴታ ተጥሎበታል፡፡

### *ብሔርተኝነት እንደ ሐሳዊ ሃይማኖት*

እናም ብሔርተኝነት የራሱ አምላክ እና ነቢያት ያሉት ሐሰተኛ ሃይማኖት መሆኑን ማየት እንችላለን፡፡ ለምሳሌ ፊርደውሲ ለኢራናዊያን ብሔርተኞች ነብይ ነው፡፡ ይህ እምነት የራሱ መለያ ምልክት፣ ጣዖታት፣ ተምሳሌቶች፣ ክብረ በዓል እና የስነ ምግባር ደንቦች አሉት፡፡ ምዕራብያውያን ብሔርተኝነት የሚሉትን እምነት የፈጠሩት በሰዎች ደመ ነፍሳዊነት ስር ባለው አርበኝነት ላይ ሲሆን ወደ ምስራቅ አሻግረውታል፡፡

## *ብሔርተኝነት እንደ ከፍተኛ ጎሳዊ ስርዓት*

በጎሳ ስርዓት ውስጥ አንድነት የተመሰረተው በደምና መሬት ትስስር ላይ ነው፡፡ ለትክክለኛነት እና ስህተት ወይም ጨዋነት፣ ሐቀኝነት እና እምነት ደንታ የለውም፡፡ የጎሳ አባል ለሆነ በሙሉ ፍቅርና እንክብካቤ ሲሰጠው፣ አባል ያልሆነው ደግሞ እንደ እንግዳ ፍጡር ይቆጠራል፡፡

በዚህ በኩል ብሔርተኝነት ተመሳሳይነት አለው፡፡ በጎሰኝነት ስርዓት ውስጥ ሰላም የሚሰፍነው ሆነ ጦርነት የሚካሄደው ለጎሳው ሲባል ነው፡፡ አንድ ሰው የጎሳው አባል በመሆኑ ብቻ ኩራት ሊሰማው፣ ሌሎች ከእርሱ ጎሳ አባል ውጭ በመሆናቸው ብቻ ይንቃቸዋል፡፡ ጎሳ በጥላው ስር ላሉ አባላቱ የደህንነት ስሜት ይሰጣል፡፡ ብሔርተኝነትም ተመሳሳይ ስሜት ያነሳሳል፡፡

የተወሰኑ የቶተሚዝም የጎሳ ስርዓት አላባውያን ወደ ብሔርተኝነት ገብተዋል፡፡ ምንም እንኳ *ሰንደቅ ዓላማ* የዘመናዊው ሰው ታላቁ ምልክት ቢሆንም፣ የተወሰኑ ስብስቦች ለአንበሳ (የእግሊዞች ምልክት) እና ሰማያዊ ባንዲራ ይዋጋሉ፤ ሌሎች ደግሞ ለንስር (የጀርመኖች ምልክት) እና ቀይ ባንዲራ ይዋደቃሉ፡፡ ከጎሳ ስርዓት ጀርባ ቶተሚዝም ቢኖርም፣ ዛሬም አገራት ተመሳሳይ ሚና ይቀበላሉ፡፡

## ምዕራፍ አራት፡ የብሔርተኝነት ኢምክንያታዊነት

*"ብሔርተኝነት በሳይንሳዊ እና ምክንያታዊ መጠይቅ ሊጠየቁ በማይችሉ፣ ነገር ግን በተከታዩች ጭንቅላት ውስጥ ትክክለኛ በሆኑ በጣት በሚቆጠሩ ቀኖናዎች ላይ የቆመ እምነት ነው።"* ኸርበርት ሉቲ (Herbert Luthy)

ከቱርክ፣ ኢራን እና ዐረቢያ እስከ አፍሪካ፣ አውሮፓ እና ኤስያ ጥግ ድረስ እስካሉት ሰዎች ድረስ የዓለማችን ህዝቦች ይለያያሉ። ልዩነታቸው የቀለም፣ የገጽታ፣ የቋንቋ እና የአካላዊ ቅርጽ ብቻ አይደለም። የወግ፣ የትውፊት፣ የባህል እንዲሁም የአስተሳሰብ ዘዬ እና የመንፈሳዊ እና ስነ ልቦናዊ መዋቅርም ጭምር እንጂ።

የተለያዩ አይነት ሰዎችን በማህበራዊ ስብስብ ስናደራጅ ቀለም፣ ዘር፣ የመልክዓ ምድራዊ ጠባይ እና ክልላዊ ድንበሮች የማንነት ልዩነት ለማበጀት በብቸኛ መስፈርትነት እንደሚበቁ ወይስ ባህላቸውን ታሪካዊ ዳራቸውን፣ ባህላዊ መለያዎቻቸውን እና ሌሎች ነገሮችን አብረን ማየት ይኖርብን እንደሆነ ማየት አለብን።

ብሔርተኝነት ህዝብ በሚያስፈጥር ፓለቲካዊ መለኪያ ስር በተሰባሰቡና በተሳሰሩ የሰዎች ስብስብ ውስጥ በሚፈጠር የጋራ ስሜትና ጥቅል ንቃተ ህሊና ውስጥ ህልው ይሆናል። ይህ የጋራ

ንቃተ ህሊና አሁን ባሉት ህያው አባላቱ እና በአያት ቅድመ አያቶች መሃከል ጠንካራ ውስጣዊ ትስስርና ስምምነት ይፈጥራል፡፡ በአባላቱ መሃከል እና ከሌሎች ህዝቦች ጋ ስለሚኖራቸው የዝምድናና የግንኙነት ጠባይ ይወስናል፤ እንዲሁ ሊያሳኳቸው በሚጓጓቸው እና በተስፋቸው መሃከል ህብር ይፈጥራል፡፡

ብሔርተኝነት ተወልዶ በፋፋበት የምዕራቡ ዓለም ታዋቂ ብያኔ መሰረት፣ ይህ የጋራ ንቃተ ህሊና የክልላዊ እና ዘራዊ መለያዎች፣ የጋራ ቋንቋ፣ ልዩ በሆኑ የባህል መለያዎች፣ የታሪክ ውርስ እና የጋራ ዕሴቶች ቅድመ ሁኔታዎች ውጤት ነው፡፡ ስለግለሰባዊ እና ማህበራዊ ባህሪይ ጠለቅ ያለ ግንዛቤ እንደሚጠቁመው ከላይ የተጠቀሱት ምክንያቶች የጋራ ንቃተ ህሊና ለመፍጠር መሰረታዊ እና በቂ ሚና አይጫወቱም፤ በአገሪቱ ህዝቦች መሃከልም ቋሚ ጠንካራ ትስስር የመፍጠርም አቅም የላቸውም፡፡

**ቋንቋ**

በብሔርተኝነት ዘፍጥረት ቅደም ተከተል ቀደምት ሂደት ውስጥ የጋራ ቋንቋ እና ባህል የጋራ ማንነት በመፍጠር ረገድ ግለሰቦችን ለማቀራረብ እንደሚጠቅም ይታያል፡፡ በግለሰቦች መሃከል ልቦቻቸውንና ስሜቶቻቸውን ማስተሳሰሪያ ገመድ ለማቀበል፣ በውጤቱም ለጋራ እና ብሔራዊ ንቃተ ህሊና መገለጽ ያገለግላል፡፡

የ18ኛው እና 19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የጀርመን የብሔርተኝነት ት/ቤት ተወካይ የሚባሉት ኸርበት ሉቲ (1744-1803) እና ጆሃን ፊች (1962-1814) ቋንቋ እና ታሪክ ለአንድ ህዝብ ብሔራዊ ማንነት እጅግ አስፈላጊ አላባውያን ናቸው ብለዋል፡፡ በተለይ ለቋንቋ፣ ለብሔራዊ መንፈስና አንድነት ልዩ ቦታ ሰጥተውታል፡፡ የሙስሊሙ ዓለም ብሔርተኞች የቱርኩ ናሚ ከማል፣ የግብፁ ናዲም የጀርመናዊያኑን ፈለግ ተከትለው ቋንቋን የብሔርተኝነት መሠረት አድርገው ወስደዋል፡፡ ነገር ግን እውነታው የጋራ ታሪክና ቋንቋ ብሔራዊ ንቃተ ህሊናን ለመፍጠር በቂ ሆነው አለመገኘታቸው ነው፡፡

ያለፉ ህዝቦችን ታሪክ ስናጠና የጋራ ቋንቋ የብሄርተኝነት መነሻ አላባ ሳይሆን የህዝብነት (nationhood) ውጤት ሆኖ እናገኘዋለን፡፡ ህዝብን ከፈጠሩ ስብስቦች መሃከል አንዳችውም በዘፍጥረት የመጀመሪያ ሂደታቸው የጋራ ቋንቋ አልነበራቸውም፡፡ ሰዎች በአንድ ክልል ውስጥ አብረው መኖር ከጀመሩ እና በስሜት ከተሳሰሩ በኋላ ባላቸው ታሪክ ውስጥ ነበር የጋራ ቋንቋ ያዳበሩት፡፡

በዘመናት ዝግመታዊ ሂደት የጋራ ቋንቋቸው ሰዋሰዋዊ መርሆዎች አዳብሯል፡፡ የአንዱ ስብስብ ቋንቋ ከሌሎች ስብስቦች ቋንቋዎች ጋ በሂደት ባደረገው ግንኙነት በርካታ ለውጦችን አድርጎ አሁን ያለበትን አቋም እስኪይዝ ያለማቋረጥ ሲለወጥ ኖሯል፡፡

በህዝብ ታሪክ ውስጥ የተወሰነ ዘመን ክስተት ካለ፣ ለምሳሌ የነጻነት ትግል በሚካሄድ ወቅት አንድ ቋንቋ ወይም የተወሰነ ባህል ብርቱ

መገለጫ አግኝቶ የህዝቡ ፍላጎት መገለጫ ይሆናል- በህንዶች የነጻነት ትግል ውስጥ ሂንዲ፣ በአልጀሪያ የነጻነት ታሪክ ደግሞ ዐረብኛ እንደሆኑት፡፡ እነዚህ አጋጣሚዎች ግን አላፊ ናቸው፡፡ በዚህ ጉዳይ ቋንቋ ህዝብ በጋራ እንዲንቀሳቀስ ስለሚያነሳሳ ይጠቅማል፡፡

በጆርጅ ዋሺንግተን ዘመን የነበሩት አሜሪካውያን ከእንግሊዞች ጋ የጋራ ቋንቋ እና ታሪክ ይጋሩ ነበር፡፡ ነገር ግን ከእንግሊዝ ተገንጥለው ራሳቸውን የቻሉ ህዝቦች ሆነዋል፡፡ ስዊዘርላንድ በውስጧ ባሉ ሶስት ክልሎች የሚነገሩ ሶስት ቋንቋዎች አሏት፤ ሆኖም ብሔርተኝነት ስሜቱ ጠንካራ ነው፡፡

የጋራ ቋንቋ መኖር የአንድነት እና የወንድማማችነት ሂደቱን በማፋጠን ረገድ ያለውን ሚና መካድ አንፈልግም፤ ምክንያቱም ቋንቋ የመግባቢያ መሳሪያ እንደመሆኑ፣ የጋራ ስነ ጽሁፍ ያስገኝልናል፡፡ ለማለት የተፈለገው፣ ምንም እንኳ ቋንቋ ብሔርተኝነት በመስራት ረገድ ሂደቱን ቢያቀላጥፈውም መሰረታዊ ሊሆን ግን አይችልም፡፡ በርካታ አገራት የተለያዩ ቋንቋ ተናጋሪዎች ሆነው ጠንካራ አገር/ክልል መመስረት እንደቻሉት፣ ተመሳሳይ ቋንቋ እየተናገሩ የሰማይና ምድር ያህል የተራራቁም አሉ፡፡ በመሆኑም ቋንቋን የብሔርተኝነት ፅኑ መሠረት ሊሆን አይችልም፡፡ ናስር እና ሌሎች የዐረብ ብሔርተኞች ቋንቋን መሰረት አድርገው የዐረብ ህዝብን ለመመስረት ጥረት ቢያደርጉም አልተሳካላቸውም፡፡ የሊባኖሶቹ ማኖናዊ ክርስትያኖች እና ሙስሊሞች ተመሳሳይ ቋንቋ ተናጋሪዎች ቢሆኑም ለስድስት ዓመታት ተዋግተዋል፡፡ በተጨማሪም ክርስቲያኖቹ

ከዐረቦቹ ወንድሞቻቸው ይልቅ አውሮፓውያኑ ይቀርቡናል ብለው ያስባሉ፡፡

በዚህ ላይ በእያንዳንዱ አገር በርካታ ቋንቋዎች ይነገራሉ፡፡ ዘዬ ሲጨመር ቁጥሩ ይበዛል፡፡ የመካከለኛው ምስራቅ ዐረቦች ሊቢያኖች የሚናገሩትን ዐረብኛ አስር ፐርሰንት እንኳ አያውቁም፡፡

እነዚህ ሁሉ እውነታዎች የሚያሳዩን ቋንቋ ብሔርተኝነት ሊቆምበት የማይችል የአሸዋ መሰረት ነው፤ በዚህ ላይ መመስረት ኢምክንያታዊ እና ደካማነት ይሆናል፡፡

## ዘር

የታሪክና ሶሽዮሎጂ ጥናቶች እንደሚያሳዩት ሁሉም የሰው ዘሮች- በተመቻቸ ማህበራዊ እና የስነ ምግባር ሁኔታዎች ውስጥ- ሁሉንም ሰዋዊ ባህሪያት የማዳበር አቅም አላቸው፡፡ እንደምናውቀው ከእስልምና በፊት የነበሩት ዐረቦች የአክራሪነት ውጤት በሆኑት በሁሉም አይነት ቅይድ አስተሳሰቦች፣ የጎሳ ግጭቶች፣ አለመግባባቶች እና ባዕድ አምልኮ መቅሰፍቶች የተመቱ ነበሩ፡፡ ነገር ግን እስልምናን ከተቀበሉ በኋላ የሞራል ዕሴቶችን ሲያዳብሩ፣ የተወሂድን አብዬታዊ መንፈስ ሲላበሱ፣ በማህበራዊ ፍትህ የማይደራደሩ ሲሆኑ በሰው ልጆች ታሪክ ውስጥ ሊታይ በማይችል ሁኔታ የስልጡንነት እና ዘመናዊነት ቁንጮ ሆኑ፡፡

ከዛ በኂላ ጥንታዊ የዘር ቅይድ አስተሳሰባቸው ዳግም ጭንቅላቱን አነሳ፣ ይህ የሆነው በእስልምና የፋፋው የተውሂድ፣ የሞራል እና ማህበራዊ ዕሴቶች በመኮስመኑ ብቻ ነው። ይህ የሚያመለክተው የማይለወጥ እና ፅኑ የሚባል ህዝባዊ መለያ እንደሌለ ነው። እንደውም ሁሉም ከዘር የሚመነጩ መለያዎች እና ተጽዕኗቸው በማህበራዊ እና ሞራል ሁኔታዎች ተቀያያሪ ናቸው። ለዚህ ሐቅ ምሳሌው የአልጄሪያ ህዝብ ነው።

የሚፈለጉትን ማህበራዊ እና የሞራል ሁኔታዎች ለመጠበቅ የሚያግዙ ነገሮችን እና ከባቢዎች እንዲሁም ጭራሽኑ መጠበቅ ይቻላልን የሚሉት ጥያቄዎች እየተነጋገርን ካለንበት ጭብጥ አድማስ ክልል ውጭ ናቸው።

ሆኖም የተወሰኑ የዘር መለያዎች በህዝቦች ታሪክ ውስጥ ዕድገታቸውን እና ልማታቸውን በማረቅ ወይም ለንቅዘታቸውና ውድቀታቸው መንስኤዎች በመሆን ወሳኝና ውጤታማ ሚና እንደሚጫወቱ መቀበል ይቻላል። ይህን ሚና መቀበል ማለት ግን ሰዎችንና አስተሳሰባቸውን በማቀራረብ የጋራ ንቃተ ህሊና ለመፍጠር ውጤታማ ናቸውን አያስይዝም።

በተደጋጋሚ እንደተስተዋለው በዘር መለያዎች የተፈጠሩ የጋራ አላባውያን የመተሳሰሪያ እና ማቀራረቢያ ምክንያት እና የብሔራዊ አንድነት መጠበቂና የጋራ ንቃተ ህሊና መፈጠር መንስኤ መሆን ይልቅ ለውስጣዊ ሽኩቻና ጥላቻ ወይም የደካማ ያልተረጋጋ እና ለጥቃት የተመቸ ህዝብ መፍጠሪያ ይሆናሉ።

ቀደሞውኑ የጦርኝነት መለያ ያላቸው እና በቋሚ ጦርነት ሌሎች ህዝቦችን በማጥቃትና በመዝረፍ፣ በመጨቆን ውስጥ ያሉ ህዝቦች፣ በታሪክ ግንኙነታቸው ማህበራዊ እና የሞራል ዕሴት ያለው ሃይል ጣልቃ እስካልገባ ድረስ ደካማ እና ልፍስፍስ ህዝቦች መሆናቸው አይቀርም፡፡

> **የአላህንም (የማመን) ገመድ ሁላችሁም ያዙ፤ አትለያዩም፤ ጠበኞችም በነበራችሁ ጊዜ በናንተ ላይ (የዋለዉን) የአላህን ጸጋ አስታውሱ፤ በልቦቻችሁም መካከል አስማማ፤ በጸጋዉም ወንድማማቾች ሆናችሁ፤ በእሳት ጉድጓድ አፋፍም ላይ ነበራችሁ፤ ከእርስዋም አዳናችሁ፤ እንደዚሁ ትመሩ ዘንድ አላህ ለናንተ አንቀጾች ያብራራል። (3:103)**

በተቃራኒው እርስ በእርሳቸው ብቻ ሳይሆን ከአኗኗራቸውና ከአባቢያቸው ጭምር ጋ፣ እንዲሁም ከሌሎች ህዝቦች ጋ የሰላማዊነት እና ተላማጅነት ባህሪይ ያዳበሩ- ከወራሪ ጠላቶቻቸው ጋ ሳይቀር የመቀላቀል፣  የመመቻመች እና የመከተል አዝማሚያ ያላቸው- ህዝቦች የህዝብነት ወይም የዘር አንድነት መጠበቅ አይችሉም፡፡ ምናልባት እንደነዚህ አይነት ስሜቶችን እንኳ ቢያዳብሩ ቀለም የለሽ፣ ውጤት አልባ፣ ሕይወት የሌለው እና ለድክምትና ወድቀት የተጋለጡ ነው የሚሆኑት፡፡

በመሰረቱ በአዕምሮው አመዛዝኖ ይሁን የስሜት ግንኙነት መርቶት፣ አንድ ግለሰብ ውስጣዊ ፍላጎቱን እና ጉትጎታው ለማሟላት እና ግለሰባዊ ድክመቱን ለማካስ ሌላ ሰው መፈለጉ ሁሉም ሰው ያለው ባህሪይ ነው፡፡

የአንድ ፍቅር ጥንካሬ አፍቃሪው በተፈቃሪው ውስጥ መሰረታዊ እና ቋሚ አስፈልጎቶቹን በተሟሉለት መጠን ላይ ይወሰናል፡፡ የዕለት ተዕለት ኑሯችን ለዚህ ከበቂ በላይ ምሳሌዎችን ይዟል፡፡ እንደዚሁም ሁሉ የስብስብ ማህበራዊ ውስጣዊ ትስስር እና የስሜት ህብር፣ ህብረተሰቡን የፈጠሩት አላባውያን/ንዑስ ስብስብ ሲመጋገቡና አንዱ የሌላውን ፍላጎት በማሟላት ላይ ይመሰረታል፡፡ በዚህ ጭብጥ የዘር አላባ ባለው ቋሚ መለያ እና ባህሪ ለአንደነትና ህብር የሚያዋጣው ፋይዳ የለም፡፡

## ባህል

እንደቋንቋ እና ዘር አንዱን ህዝብ ከሌላው የሚለየው በውስጡ የያዘው የጋራ ባህል ይኖረዋል፡፡ መሰረታዊው ጥያቄ ግን አንድ ህዝብ ለመመስረት ምን ያህል ውጤታማ ናቸው የሚለው ነው፡፡ ልምድ፣ ወግ፣ ባህል ያለፉ ትውልዶች የግለሰቦች ሆነ ተብሎ የተደረጉ ግንኙነቶች ውጤቶች ናቸው፡፡

ባለፉት እና ባሁኑ ትውልዶች እና በማህበራዊ ተቋሞች መሃከል ምንም አይነት ዝምድና ግንኙነት ባይኖር ባህሉ ሊተላለፍ አይችልም፡

፡ የጋራ ስሜት እና የአንድነት ንቃተ ህሊና ዕውን ካልሆነ ባህል ለሚቀጥለው ትውልድ አይተላለፍም፡፡ በመሆኑም ሁሉም የህዝብ ባህል የብሔራዊ ንቃተ ኅሊና እና በዚያ አቅጣጫ የተቅጣጨ የሰዎች እንቅስቃሴ ውጤት ነው እንጂ፣ የህዝብ መሰረትም ወይም ምንጭ ሊሆን አይችልም፡፡

በአሁንነት ውስጥ የአንድ ህዝብ ባህል ሁለት አይነቶች ናቸው፡፡ (1) ፍትሃዊ እና መልካም የሰው ለሰው ግንኙነት ለመመስረት፣ ያለፈው ትውልድ ለከፍተኛ የሞራል ዕሴቶች ልዕልና ያደረጋቸው ድንቅ ትግል ውጤቶች፤ ሁሉንም የሰው ልጆች የታፈሩ እሴትን ያቀፈ

(2) ከድንቁርና እና ለዓለማዊ ጥቅም ካለ ገደበ የለሽ ፍላጎት የመነጩ እና ከኢፍትሃዊ የማህበራዊ ግንኙነቶች የተነሱ፡፡

የመጀመሪያው አይነት ባህል ለሕይወት እድገት እና ብልጽግና መቀጠል ምክንያት ሲሆኑ፣ ሁለተኛው ወደ ውድቀት፣ የኒሊዮሽ፣ ባርነት እና ህዝብ ማታለል የሚያመሩ ሆነው ገዢዎች እና ባለፀጋዎች እጅ ውስጥ የሚገኙ መሳሪያዎች ናቸው፡፡

ፍትህ፣ አምላክን እና መልካም እሴቶችን ጠባቂነት እንዲሁም ልማት የሕይወት፣ በጎነት እና ጤናማ ባህል ህያው ማድረጊያ መሣሪያዎች እንደመሆናቸው፣ ለአንድ ህዝብ መረጋጋት እና ጥንካሬ፣ ህያውነት መሠረት ይሆናሉ፡፡ በሌላ በኩል ያልተፈለጉና ጤናማ ያልሆኑ ባህሎች ለህዝብ ውድቀት እና ለጥፋቱም መንስኤ ይሆናሉ፡፡ በታሪክ

ካገኘናቸው የሎጥ፣ ዐድ፣ ተሙድ፣ ጥንታዊቷ ግብፅ እና ግሪክ አንስቶ በአሁኒቷ ዓለም ውስጥ የሚታዩትን ህዝቦች በመመልከት ከበቂ በላይ ምሳሌዎችን ማግኘት ይቻላል፡፡

እንደ መርህ፣ ህይወት ያላቸው ነገሮች እንቅስቃሴ ከተፈጥሯዊ ገደቦች፣ ውጫዊ የአካባቢ ሁነቶች እና ውስጣዊ የደመ ነፍስ ፍላጎቶች ወደ ነጻነት የሚደረግ ጉዞ ነው፡፡ ከረጅሙ የዝግመተ ለውጥ ሂደት ውስጥ በመጀመሪያ ብቅ ያለው ቀደምት ሰው ከተፈጥሮ ቀንበር ነጻ የወጣው ነበር፡፡

ሆኖም ይህ ነጻነቱ የተሟላ አልነበረም፡፡ እርሱ ብቅ ከማለቱ በፊት ከነበሩት እንስሶች ግን የተሻለ ነበር፡፡ ጥንታዊው ሰው ከውስጥም ከውጭም ሥራ ላይ ባሉ ሃይሎች፣ በደመ ነፍስ እና ተፈጥሮ የተገዛ ነበር፡፡ በሂደት ንቃተ ህሊና ሲያዳብር፣ የነጻ ፈቃዱን ጡንቻዎች ሲያፍታታ አካላዊ እና ደመ ነፍሳዊ ወሰኖቹን እየጣሰ የተሻለ ነጻነት ተቀዳጀ፡፡

የሰዎችም ማህበራዊ ግንኙነት ተመሳሳይ ሂደት ነበር የተከተለው፡፡ ህብረተሰብ በቀደምት ዘፍጥረት ደረጃው ወቅት ሰዎች አንዳቸው ከሌላቸው የፈጠሩት ግንኙነት በውስጣዊ ግፊት እና አካላዊና አካባቢያዊ አላባውያን ማነቆዎች የታፈነ ነበር፡፡ በጥንታዊ ህብረተሰብ ውስጥ የአካባቢያዊ እና አካላዊ ሁነቶች፣ ተከትሎም ስሜታዊ፣ ቤተሰባዊ እና ጎሳዊ ግንኙነቶች ማህበራዊ ንቃተ ህሊናን ለማዳበር መሰረታዊ መሳሪያዎች ነበሩ፡፡

ነገር ግን ባደጉ እና በለሙ ህብረተሰቦች ውስጥ ማህበራዊ ንቃተ ህሊናን ለማዳበር እና ለማስተካከል አዳዲስ አላባውያን ዕውን ሆነዋል፡ ፡ በህብረተሰብ አባላት መሃከል ያለውን ማህበራዊ ግንኙነት በማሳለጥ ረገድ፣ አካባቢን ጨምር አካላዊ አላባውያን ያላቸው ሚና እየቀነሰና አስፈላጊነታቸው እየተዳከመ መጥቷል፡፡

አሁን ላይ በተመሳሳይ አካላዊ እና ጂኦግራፊያዊ ሁነት ውስጥ የሚኖሩ ታላላቅ መንግስታት እና ህዝቦች ተስማምተው አንድ ህዝብ ፈጥረው ብቻ አይደለም ያሉት፤ በፍጥጫም፣ አንዳንዴም በግጭት ውስጥ እየኖሩ ነው፡፡ በህንድ፣ በተመሳሳይ አካላዊ እና አካባቢያዊ ሁኔታ ውስጥ ሆነው ሂንዱዎች እና ሙስሊሞች ተመሳሳይ ብሔራዊ ስሜት የላቸውም፤ ለአንድ ህዝብ ትብብር አስፈላጊ የሆነውን አስተባባሪ ገመድ አጥተዋል፡፡

ተመሳሳይ ምሳሌ በእንግሊዞች እና አየርላንዶች መሃከል እናገኛለን፡፡ ምንም እንኳ ተመሳሳይ የታሪክ፣ ማህበራዊ እና ቋንቋ ውርስ ቢኖራቸውም አንድ ህዝብ ሊያደርጋቸው የሚያስችላቸውን የአንድነት እና የመግባባት መንፈስ ሊያዳብሩ አልቻሉም፡፡ በተቃራኒው በሶስተኛው ዓለም አገራት መሃከል፣ በሺዎች ኪሎ ሜትሮች ተራርቀው በተለያዩ አካላዊና እና አካባቢያዊ ሁነቶች ውስጥ እየኖሩ፣ በጉልህ የሚታይ የቋንቋ፣ ዘር እና የታሪክ ልዩነት ያላቸው ህዝቦች ጥብቅ የወንድማማችነት ስሜት ዳብሮ ይታያል፡፡ ለምሳሌ አልጄራውያን ከኩባ እና ቬትናም ወይም ፍልስጤማውያን ጋ የአንድነት ስሜት ነበራቸው፡፡

## ብሔርተኝነት፣ ራሱን የሚያመክን ዕሳቤ

የብሔርተኝነት ዓላማ አንድነትን መፍጠር ቢሆንም ውጤቱ ግን ተቃራኒው ሆኖ የራሱን ግብ ያመክነዋል። በህዝብ አባላት መሃከል የአንድነት ስሜትን ለኩሰው ያፋፍማሉ የሚባሉት መሠረቶች ቋንቋ፣ ዘር እና ባህል በዋነኝነት ይቆጠራሉ።

ነገር ግን በሁሉም አገራት የዘር እና ቋንቋ ህዳጣውያን አሉ። እነዚህ ህዳጣውያን በብዙሃኑ ኘሮፓጋንዳ የሚቀነቀነው ብሔርተኝት ስሜት ጋ ሲፋጠጡ ግላዊ መለያቸውን የማጣት አደጋ ስለሚሰማቸው ተቃውሞ ያነሳሉ። መሬት ላይ ባለው ሐቅ፣ በተደጋጋሚ እንደሚታየው በብዙሃኑ የሚቀነቀነው የብሔርተኝት ስሜት በህዳጣውያን ዘንድ ክልላዊ፣ ዘራዊ ወይም የቋንቋ ብሔርተኝነት ቀስቀሶ በአገሪቷ ውስጥ የልዩነት እና ግጭት መንስኤ ሲሆን ይስተዋላል።

አመክንኗዊ ጥያቄም ማንሳት ይቻላል፤ ለምን የብዙሃኑ ብሔርተኝነት ስሜት ትክክል ሆኖ ወደፊት ሲገፋ፤ የህዳጣውያኑ ደግሞ ስህተት ሆኖ እንደሚተው አሳማኝ ምክንያት ማቅረብ ይቻላል? ለምን የእንግሊዝ ብሔርተኝነት ትክክል ሆኖ ይደምቃል፤ የአየርላንድ ይኮነናል? የኢራቅ ባዝ ፓርቲዎች የዐረብ ብሔርተኝነት ሲያቀነቅኑ ትክክል ሆነው የኩርዶች እንደስህተት ተቆጠረ? ለምንስ በየአገሩ ተበታትነው በሚገኙ ኩርዶች ውስጥ ያለው የብሔርተኝነት ስሜት እንደ ስህተት ተቆጥሮ ውርጅብኝ ይወርድባቸዋል? ክልላዊ፣ ዘራዊ

እና ቋንቋዊ ቅድ ዕሳቤ ለአንዱ ትክክል ከሆነ ለሌላውም ትክክል መሆን አለበት፤ ስህተቱም እንዲሁ። ለሁለቱ የተለያዩ መመዘኛዎች ማቅረብ አንችልም። የነጭ አሜሪካውያን ብሔርተኝነት ጥሩ ሆኖ የጥቁሮቹ መጥፎ የሚደረግበት ምንም ምክንያት የለም።

ብሔርተኝነት ምንም አይነት አመክኗዊ መሰረት እንደሌለው ማየት ይቻላል። ሌላ ሃይል ሳይመጣ ግቡን ራሱ ያመክነዋል፤ ከአንድነት ይልቅ ልዩነትን ፈጥሮና አፋፍቶ ያርፈዋል። በመጨረሻም ሃይል ይጠቀማል፤ ይህም ተጨማሪ ቅሬታንና ግጭትን እንዲሁም ዕልቂትን ያስከትላል።

ብሔርተኝነት የዘር፣ የቋንቋ እና ባህል ህዳጣውያንን ተቃርኖ ፈትቶ አያውቅም። ከሆነ ዘር መወለድ ወይም የሆነ ቋንቋ መናገር ተለዋዋጭነት ውስጥ ሊካተት ስለማይችል፣ ሁሌም ህዳጣውያን ሆነው ስለሚቀሩ የብዙሃኑን ስሜት መጋራት አይችሉም። በስደት ወይም በድንበር መስፋፋት ወይም በወረራ በአንድ አገር ውስጥ የተጠቃለሉ ህዝቦች፣ በርካታ ዓመታት ወይም ብዙ ትውልዶች ቢያልፉም ራሳቸውን የተገለሉ ወይም እንግዳ ስብስብ አድርገው ይመለከታሉ። ብዙሃኑም እነርሱን በተመሳሳይ ስሜት ይመለከቷቸዋል። በቱርክ፣ ሶሪያ፣ ኢራን ያሉ አርመናውያን፣ ኩርዶች፤ ስኮትላንዳውያን፣ አየርላንዳውያን እና የአሜሪካ ጥቁሮች ለዚህ ግልጽ ምሳሌ ናቸው።

## ምዕራፍ አምስት፡ የብሔርተኝነት አደጋ

ከብሔርተኝነት ታላላቅ አደጋዎች መሃከል ዋናው በራስ መታበይ፣ አንድ ግለሰብ ወይም ስብስብ እጅግ ራስ ወዳድ ከመሆኑ የተነሳ እውነታን ክዶ፣ ጨካኝና ግትር መሆን ነው፡፡

የብሔርተኝት ስሜት አብዛኛውን ጊዜ በሌላው ህዝብ ላይ ቅይድ ዕሳቤ ሲያዳብር ይታያል፤ ከስነ ህብረተሰብ ቋንቋ ለመዋስ፣ የ"እኛ ስብስብ" ወይም የ"እኔ ስብስብ" ስሜትን በማዳበር፣ የእኔ ለሚለው ህዝብ እና ለየትኛውም አይነት ተግባሩ ፍቅር እና አድናቆት ሲቸር፣ ከርሱ ውጭ እና ሌላ ለሚለው ስብስብ ያልተገደበ ጥላቻ ያሳድራል፡፡ ራስን እና የእኔ ስብስብን ማመፃደቅ እና ለሌሎች የማዘን እና የመቻቻል ስሜት መጥፋት ገዥ ህግ ይሆናል፡፡

ይህ በራስ የመታበይ የብሔርተኝነት ጡዘት በተለያዩ መንገዶች ራሱን ይገልጻል፡ በዘር እና በዘር ጥራት መታበይ፣ ትምክህተኝነት፣ ዘረኝነት ወ.ዘ.ተ

### የትምክህተኝነት ኮምፐሌክስና ታሪክን ማንሻፈፍ

ታዋቂው ሶሾሎጂስቱ ዋልተር ሌኪዩር (Walter Lacquer) ሲጽፍ "ከብሔርተኝነት መለያዎች መሃከል ለራስ ህዝብ የተጋነነ ግምት መኖርና ሌሎችን ውዳቂ ማድረግ፤ ራስን ያለመሄየስ፣ ለሌሎች

የሃላፊነት ስሜት ማጣት እና ለሌሎች ፍትሃዊና ርትዕ አለማስፈን ዋና ዋና ናቸው፡፡ ብሔርተኝነት ዕውነታን ዘንግቶ ሌሎችን የመጫን ምናባዊና ወጋዊ ራዕይ ያዳብራል፡፡"

ራስን ለማላቅ ሲል ብሔርተኝነት አብዛኛውን ጊዜ ወደ አጉል እምነት፣ ግነት፣ በህፀፅ የተሞላ ሃሳብ ወደ ማቅረብ፣ ሌሎችን ማበሻቀጥ እና ያልተገባ ራስን ማወደስ እና ከሁሉም የከፋው *የተጣመመ ታሪክ፣ አርኢያ እና ተረቶች መፍጠር* ውስጥ ያዘፈቃል፡፡ የታሪክ እና ማህበራዊ ዕውነታን ስለሚፈራ ታሪካዊ ሀቆችን ወደ ምናባዊ ወግ ይለውጣል፡፡

ዊል ዱራንት "በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ብሔርተኝነትን አስገኘ፡፡ ብሄርተኝነት ደግሞ ሁሉንም የታሪክ ሰዎችን አነቀዘ" ብሏል፡፡ ትሬይልስችኬ፣ ቮን ሲባል፣ ሚሺሌ፣ ማርቲን፣ ማክካውላይ፣ ግሪን፣ ባንደርፍት እና ፊቲክ፤ ሁሉም በቅድሚያ ብሔርተኞች፣ ከዚያ የታሪክ ሰዎች ነበሩ፡፡ ሁሉም ብሔርተኛ አገሩን/ክልሉን በእግዜር የተመረጠች አድርጎ ሌላውን በሃጢያተኞች እና አረመኔዎች የተሞላ አድርጎ ይቆጥራል፡፡

ብሔረተኝነት ታሪክን እጅግ ከማበላሸቱ እና በማይረቡ ጫጫታ የተሞላ ከማድረጉ የተነሳ፣ አንድ ብልህ ሰው *"ሁሉን አቀፍ ሰላም ዕውን ለማድረግ የወዳጅነት እና የንግድ ስምምነቶችን ከማድረግ ይልቃ ታሪክን መተው ይሻላል"* ብሎ መክሯል፡፡

ታሪክ ማጣመም ከብሔርተኝነት ታላቅ ጉዳቶች መሃከል ዋናው ነው፡ ፡ ይህ ትክክል የሚሆነው እጅግ ለአክራሪ ብሄርተኝነት ነው ብሎ

መከራከር ይቻላል። ነገር ግን ጉዳዩ እንዲያ አይደለም። በየትኛውም አይነት ደረጃ ላይ የሚገኝ ብሔርተኝነት በምንነቱ ራስን ዕቡይ ማድረግ እና ሌሎችን ወደ ማጠልሸት ይዘነበላል። በህዝብ ውስጥ ስሁት የኩራት መንፈስ ማስረጽ እስካልቆመ ድረስ ብሔራዊ ዕቡይነት ከራሱ ይልቅ ሌሎችን ወደማስቀደም ማዞር ይቻላል?

## ዘረኝነት

ብሔርተኝነት ከመልካም ዕሴት እና ምክንያታዊነት ይልቅ፣ በሰው እንሳሳዊ የደም ነፍስ ፍላጎት ላይ ስለሚመሠረት ዘረኝነት አንዱ መሠረታዊያኑ እና መለያው ነው።

ብሔርተኝነት ግለሰቦችና ስብስቦች ከአንድ ብሔር ውስጥ በድንገቴ መፈጠሩ እና መገኘቱ እንዲኮራ እና ሌሎችን በጠላትነት፣ በዝቅተኝነት መንፈስ እንዲመለከታቸው የተሳሳተ ሃሳብ ያስጨብጣል። አንድ ሰው ነጭ ቆዳ ስላለው ብቻ ጥቁሮችን ዝቅ አድርጎ እንዲያይና የስራ ዕድል እንዲነፍጋቸው ያደርጋል። አነስታይንን የመሰለ ብሩህ ሰው አይሁድ ስለሆነ ብቻ ይጠላል። በፈንሳይ ወይም ጀርመን መወለድ ሆን ተብሎ በምርጫ የሚገኝ ሳይሆን የድንገቴ ውጤት ነውና ሌሎችን ለመጥላት ወይም ለራስ እና ለሌላው የተለያዩ መመዘኛዎችን አውጥቶ የተለያዩ ፍርድ ለመስጠት ምክንያት ሊሆን አይገባውም።

አንድን ወንጀለኛ እና ደንታ ቢስ ሰነፍን የራስ ወገን ስለሆነ ብቻ፣ ከሌላ ህዝብ የተገኘን ሃላፊነት የሚሰማውን፣ ቸር እና ምርታማ ሰው በላይ አድርጎ እንደመምረጥ ምን ኢሰብአዊና ኢምክንያታዊ ነገር ሊገኝ ይችላል?

አንድ ሰው በዘሩ፣ ስራዎቹ፣ ዕሴቶቹ ወይም አመለካካቱ ግጭት ውስጥ ሳይገባ  ቋንቋው እና አገሩ/ክልሉ ከሌላ በመሆኑ ብቻ መጤ ወይም እንግዳ ተብሎ ይጠራል። አንድ ሰው የሆነ መሬት ወይም ህዝብ መሃከል ስለተወለደ ክብር እና መልካም ስራ ሁሉ ገደል ይገባሉ። የአንድ ግለሰብ መለኪያ ሚዛኖች ድርጊቱ፣ መልካም ዕሴቶቹ፣ ጨዋነቱ ወይም ሃላፊነት የሚሰማው መሆኑ ቀርቶ ክልል/ድንበር እና ደም ይሆናሉ።

ብሔርተኝነት እየገነነ ሲመጣ የተከታዩ ዕይታ አጭርና ጠባብ እየሆነ ይመጣል። አንድ ብሔርተኛ ብሔሩን/አገሩን ያለዕውቀት እና ማስተንተን መደገፍ ይጀምራል። ከህዝቡ ውጭ ያለውን ነገር በሙሉ እንግዳና ድንቁርና ብሎ ይወስደዋል። ትክክል እና ስህተት ትርጉም የለሽ ፅንሰ-ሃሳቦች ይሆናሉ።

ብሔርተኝነት መጨረሻው ዘረኝነት መሆኑ ጥያቄ አይነሳበትም። በየትኛውም ቦታ ያለን አንድን ስብስብ የተለየ አድርጎ ለማቅረብና የራሳቸውንን ስያሜ ለመስጠት፣ የዚያን ስብስብ አባላት በዘር፣ ደም ወ.ዘ.ተ መለኪያዎች ከሌላው የበለጡ መሆናቸውን ማሳመን ግድ ይላል። እንደዚሁም ሁሉ ሌሎች ጎረቤት ህዝቦችም ተመሳሳይ ስሜት

ስለሚያዳብሩ ማብቂያ በሌለው ግጭት፣ ተቀናቃኝነት እና የዘረኝነት ጥላቻ ውስጥ ይዘፈቃሉ።

ሁልጊዜም ብሔርተኝነት ወደ ዘረኝነት እንደሚያመራ ታሪክ ይመስክራል። እነዚያ ባለምጡቅ ጭንቅላት ባለቤት የሆኑት ግሪኮች በስልጣኔ ማማ ላይ ሆነው ግሪክ ያልሆኑትን “አረመኔ” እያሉ ነበር የማጠሯቸው። አሪስጣጣሊስ እንዲህ ይላል “አረመኔዎቹ የግሪክ ባሪያ መሆናቸው የተፈጥሮ ፈቃድ ነው።” አይሁዶቹ ራሳቸውን በአምላክ የተመረጡ ህዝቦች አድርገው ነው የሚቆጥሩት። ሮማውያኑም በስልጣኔያቸው ማማ ላይ ሆነው፣ በምድራችን ላይ ሶስት አይነት ህዝቦች- ሮማውያን፣ ወዳጆቻቸው እና አረመኔዎች- እንዳሉ ያምኑ ነበር።

### ሌሎችን የመግዛት ሱስ

ብሔርተኝነት በሌሎች ላይ የበላይ ለመሆን እና የመግዛት ሱስ የሚያድርበት በሶስት መግፍኤዎች ነው፦

1. ጠንካራ በራስ የመታበይ ስሜት
2. የትምክህተኝነት ኮምኘሌክስ
3. በራስ ጥቅም መታወር (የሌሎችን ጥቅም ወደ ጎን ገሸሽ ማድረግ)

አንድ ብሔርተኛ ስብስብ አስተሳሰቡ በራስ ጥቅም ዙሪያ ብቻ ስለሚሆን በሌሎች ላይ የበላይ የመሆን መብት ለራሱ ይሰጣል።

የሚጠበቅ ውጤቱም ግጭት፣ ማጥቃት እና መቆጣጠር ይሆናል፡፡ አንዳንዶች ይህ ትክክል የሚሆነው ለአክራሪ ብሔርተኞች ነው ይላሉ፡፡ ታሪክ እንደሚያስረዳን ጤነኛ እና ጤነኛ ያልሆነ ብሔርተኝነት እንደሌለ ነው፡፡

ቀደም ባሉት ምዕራፎች እንደተገለጸው የ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የምዕራቡ ዓለም ቅኝ ግዛት መንስኤው የብሔርተኝነት ስሜት ነበር፡፡ የሁለቱ የዓለም ጦርነቶች ዕልቂትና በሂሮሺማ እና ናጋሳኪ የሆነው ጥፋት፣ እንዲሁም የሰው ልጆችን ታሪክ በደም ያጨማለቁ ሌሎች በመቶዎች የሚቆጠሩ ጦርነቶች ብሔርተኝነት ህያው ሃይል ሲሆን የሚፈጥራቸው ቀውስ ምስክር ናቸው፡፡

በብሔርተኝነት ላይ የተመሰረተ ህብረተሰብ በኋላ ቀር መመዘኛዎቹ አንዱን ከፍ ሌላውን ዝቅ፤ አንዱን ገዥ ሌላውን እንደባሪያ ዝቅተኛ የሚያደርግ ዝግ ስርአት ነው፡፡ አንድ አርአያን በምንም መልኩ ሴማዊ፤ ቱርካዊው ኢራናዊ መሆን አይችልም፤ አንዱ ሌላውን ካልተቆጣጠረው በስተቀር፡፡ በመሆኑም ብሔርተኝነት ሲስፋፋ ውጤቱ ሌሎችን ከስሩ አድርጎ መግዛት ይሆናል፡፡

## የሰውን አስተሳሰብ ማጥበብ

ብሔርተኝነት የሰውን የአስተሳሰብ አድማስ በሁለት መንገዶች ያጠባል፤ አንደኛው፣ ብሔርተኛውን ስለሰው ዘር እንዳያስብ ያደርገዋል፡፡ ስለሰው ዘር መልካምነት ደንታ ቢስ ይሆናል፡፡

የወዳጅነት መመዘኛው እና የአስተሳሰቡ አድማስ በድንበሩ/ክልሉ አጥር ይወሰናል፡፡ ሁለተኛው፣ ሰው ሃይማኖቱን፣ መንፈሳዊነትን፣ ምሁራዊነትን እንዲተው፣ በምትካቸው በመሬቱ፣ ደሙ፣ ክልሉ/አገሩ እና ዘሩ ላይ እንዲያተኩር ይገፋፋዋል፡፡ በውጤቱም የአስተሳሰብ አድማሱን ያጥረዋል፡፡

ብሔርተኞች የስሜታቸው ባሪያዎች ሲሆኑ፣ ለምክንያት ሆነ ምሁራዊነት ደንታ ቢስ ናቸው፡፡

## ምዕራፍ ስድስት፡ እስልምና እና ብሔርተኝነት

ከእስልምና በፊት በነበረው ዐረቢያ ጎሳ፣ ነገድ፣ ዘር እና ቋንቋ የትልቅነት እና አናሳነት መለኪያዎች ነበሩ፡፡ የዘመናዊው ብሔርተኝነት እና ዘረኝነት ዋልታና ማገር የሆኑት ደም እና ሥጋ በዛም ወቅት የአንድነት መሰረቶች ነበሩ፡፡ ቋንቋም እንዲሁ የታላቅነት መለኪያ ነበር፡፡ በዚህ ምክንያት ዐረቦቹ ዐረብ ያልሆኑት "አጀም"- ደንቆሮ- እያሉ ነበር የሚጠሯቸው፡፡

ገና ከጅምሩ የብሔርተኝነት ሃይሎች እና ዘረኝነት የእስልምና ፀር ሆነው በጠላትነት ቆመዋል፡፡ እነዚህ ሃይሎች ቁረይሾችንና ሌሎች ህዝቦችን የነቢዩ ጋሬጣ እንዲሆኑ አድርጓቸዋል፡፡ ቅዱስ ቁርአን ለምን ከመካ ወይም ጣዒፍ ከሆኑ የተከበሩ ሰዎች በአንዱ ላይ አልወረደም በሚል ተቋውሟቸውን አሰምተዋል፡፡

**"ይህም ቁርአን ከሁለቱ ከተሞች በታላቅ ሰው ላይ አይወርድም ኖሯልን? አሉ።"** (43:31)

የዐረብ ጎሰኞች በጠባቡ የዕይታ አድማሳቸው ለምን ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ከጎሳቸው አባል እንዳልሆኑ በቁጭት ተናዘዋል፡፡ በዚህም የእርሳቸው ጎሳ የበላይነት በሌሎች ላይ ይጭኑ ይሆን በሚል በጥርጣሬ ተመልክተዋቸዋል፡፡ አቡ ጀህል በግልጽ "እኛ ከአብድመናፍ ቤተሰቦች ጋ እኩል ነን፡፡ በፈረስ ግልቢያ ቢሆንም ከእነሱ አናንስም፤ በለጋስነትም እኩል ነን፡፡ እንዴት ሆኖ ነው እነርሱ ነቢይ ነን፤ ወህይ

ወርዶልናል የሚሉት? በአላህ ይሁንብኝ ሙሐመድን እንደ ነቢይ አንቀበለው” ብሎ ነበር፡፡

ተመሳሳይ የዘረኝነት መንፈስ አይሁዶችንም በነቢዩ ላይ እንዲነሱ አድርጓቸዋል፡፡ ለምን ነቢዩ ከይስሃቅ ዘር ይልቅ ከባርያቱ ከእስማኤል ዘር ይሆናል በሚል ተቃውመዋል፡፡ እናም ሁለቱ- አይሁዶቹና ጣዖት አምላኪዎቹ ቁርይሾች- በጋራ በነቢዩ እና ተከታዮቻቸው ላይ ተነስተዋል፡፡

በመዲና ውስጥም ቢሆን እስልምናን ለማጥቃት የብሔርተኝነትን እሳት ማንደድና ማራገብ የሙናፊቆች ዋና መሳሪያ ነበር፡፡ በአንድ አጋጣሚ ከሙናፊቆች መሪዎቹ አንደኛው የቤጋስ ጦርነትን ያልተፈታ ቁርሾ በማንሳት በሁለቱ ታላላቅ የሙስሊም ነገዶች- ኸዝረጅና አውስ- መሃከል ግጭት መፍጠር ችሎ ነበር፤ ይህን ተከትሎ አላህ የሚከተለውን አንቀጽ አወረደ

> **“እላንተ ያመናችሁ ሆይ! ከነዚያ መጽሐፉን ከተሰጡት ሰዎች ከፊሉን ብትታዘዙ ከእምነታችሁ በኋላ ከሐዲዎች አድርገዉ ይመልሱዋችኋል።”** (3፡100)

አብደላህ ኢብን አቢ፣ በመዲና የሙናፊቅ መሪዎች መሃከል አንዱ፣ ታማኝ ብሔርተኛ ሲሆን በብሔርተኝነት መንፈስ ቅኝት በቋሚነት የመዲናን ሰዎች ይጎተጉት ነበር፡፡

“የተወሰኑ ለማኞች ከሌላ ቦታ መጥተው እኛ መሬት ላይ ሠፍረው ኮርማ ሆነዋል፡፡ እኛን እንዲያጠቁን እያደለብናቸው ያሉ ውሾች ናቸው፡፡

“እነዚህን እንግዶች በሃብታችሁ እና መሬታችሁ ወዳጅ አድርጋችሁ ማቅረባችሁ ስህተት ነው፡፡ ዛሬ መርዳት ብትቆጠቡ ነገ ይፈርጥጣሉ” እያለ ይመክር ነበር የመዲና ሰዎችን፡፡

ለነዚህ ክፉ ቃላት ቅዱስ ቁርአን በሚከተለው መልኩ ምላሽ ሰጥቷል፡ ፡

> **“እነሱ እነዚያ፡- አላህ መልክተኛ ዘንድ ላሉት ሰዎች እስከሚበታተኑ ድረስ አትቀልቡ የሚሉ ናቸው፤ የሰማያትና የምድር ድልቦችም የአላህ ናቸው፤ ግን መናፍቃን አያውቁም። ወደ መዲና ብንመለስ አሸናፊው ወራዳውን በእርግጥ ከርሷ ያወጣል ይላሉ፤ አሸናፊነትም ለአላህ፣ ለመልክተኛውና፣ ለምእምናን ነው፤ ግን መናፍቆች አያውቁም።”** (63፡7-8)

የራስን ህዝብ ማምለክ (ዘረኝነት) እና የዘረኝነት ስሜት የእስልምና ቀንደኛ ጠላት እንደሆኑ አሉ፡፡ የዐረብ ብሔርተኞች የኩራታቸው ምንጭ እስልምና እና ሙስሊምነት ሳይሆን ዐረብ መሆን ነው፡፡ ግብጻዊው ፈርዖንን ያስባል፤ ቱርካዊው ከቼንጊዝ እና ሃላኩ ጋ ያለውን ግኑኝነት ለማሳየት ይሞክራል፡፡ ኢራናዊው ከሙሐመድ

(ሶ.ዐ.ወ) እና ዓሊ ይልቅ በሳይረስ፣ ዳሪየስ፣ ቡዛርጆመህር፣ ማኒ እና መዝዳክ ይኮራል፡፡ በዚህ እና ወደኋላ በሚገለፁ ምክንያቶ እስልምና እና ብሔርተኞች ጠላታ ሆነው ይኖራሉ፡፡

### ክልላዊነት/ድንበራዊነት

ብሔረተኝነት ትክክለኝነትን ከመሬት እና አገር ጋ ሲያስተሳስር፣ በእስልምና ግን ትክክለኝነት ከመሬቱ እና አገሩ ፈጣሪ እና ባለቤት ጋ ያደርገዋል፡፡ ብሔር በላቲን የትውልድ ቦታ ማለት ነው፡፡ በአንድ መሬት ላይ የተወሰኑ ስብስቦች አብሮ መኖራቸው የብሔርተኝነት ቅርጽ ይሰጣል፡፡ ያ መሬት የዛ ስብስብ ሲሆን ሌላ ስብስብ የኔ ነው ማለት አይችልም፡፡ በዛ መሬት ላይ የሚኖሩ ግለሰቦች ሕይወታቸውን ገብረው ቢሆንም መጠበቅ አለባቸው፡፡

በእስልምና መሬት የዚህ ወይም የዚያ ስብስብ ንብረት አይደለም፡፡ መሬት የአላህ ንብረት ነው፡፡ ሁሉም ሰዎች የአላህ ወኪል ናቸው፡፡ ቅዱስ ቁርአን በተለያዩ አንቀጾች ለዚህ ነጥብ አትኩሮት ሰጥቷል- የትኛውም ህዝብ በየትኛውም መሬት ላይ ሞኖፓሊ የለውም፣ ዓለም ሁሉ የአላህ ነች፡፡

> **“(ሙሐመድ ሆይ!) በል- የንግሥና ባለቤት የሆንክ አላህ ሆይ! ለምትሻዉ ሰዉ ንግሥናን ትሰጣለህ፤ ከምትሻዉም ሰዉ ንግስናን ትገፍፋለህ፤ የምትሻዉንም ሰዉ ታልቃለህ፤**

**የምትሻዉንም ሰዉ ታዋርዳለህ። መልካም ነገር ሁሉ በእጅህ (በችሎታህ) ነው፤ አንተ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነህና።"** (3:26)

**"«ምድርና በውስጥዋ ያለው ሁሉ የማን ነው የምታውቁ ብትኾኑ (ንገሩኝ)» በላቸው። «በእርግጥ የአላህ ነው» ይሉሃል።"** (23:84-85)

**"«የነገሩ ሁሉ ግዛት በእጁ የኾነ እርሱ የሚጠብቅ በእርሱ ላይ የማይጠበቅ ማን ነው የምታውቁ እንደኾናችሁ (መልሱልኝ)» በላቸው። «በእርግጥ አላህ ነው» ይሉሃል። «ታዲያ እንዴት ትታለላላችሁ» በላቸው።"** (23:88-89)

**"«እኔ አስፈራሪ ብቻ ነኝ። ኀያል አንድ ከኾነው አላህ በቀር ምንም አምላክ የለም» በላቸው። «የሰማያትና የምድር በመካከላቸውም ያለው ሁሉ ጌታ አሸናፊው መሓሪው ነው።»"** (38:65-66)

የዚህች ምድር ባለቤት እርሱ ሲሆን፤ ሰውንም የእርሱ ወኪል አድርጎታል። ስለዚህ ዓለም ለሁሉም የሰው ልጆች የተገባች ነች።

**"እርሱም ያ በምድር ምትኮች ያደረጋችሁ በሰጣችሁም ጸጋ ሊፈትናችሁ ከፊላችሁን ከከፊሉ በላይ በደረጃዎች ከፍ ያደረገ ነው።**

**ጌታህ ቅጣቱ ፈጣን ነው። እርሱም እጅግ መሓሪ ሩኅሩኅ ነው።"** (6፡165)

**"(ሙሐመድ ሆይ) ጌታህ ለመላእክት፡- «እኔ በምድር ላይ ምትክን አድራጊ ነኝ፤» ባለ ጊዜ (የኾነውን አስታውስ፤ እነርሱም) «እኛ ከማመስገን ጋር የምናጠራህ ላንተም የምንቀድስ ስንኾን በርሷ ውስጥ የሚያጠፉንና ደሞችንም የሚያፈስን ታደርጋለህን?» አሉ። (አላህ) «እኔ የማታውቁትን ነገር አውቃለሁ» አላቸው።"** (2፡30)

**"አላህ በምድር ውስጥ ያለን ሁሉ ለናንተ የገራላችሁ መርከቦችንም በበሕር ውስጥ በፈቃዱ የሚንሻለሉ ሲሆኑ፣ (የገራላችሁ) መሆኑን…"** (22፡65)

የምድራችን ስጦታ ለሁሉም ሰው የተገባ ነው እንጂ፣ የዚህ ወይም የዚያ የተለየ ስብስብ ወይም ህዝብ አይደለም።

የትኛውም ወሰን በሰው ልጆች ላይ ሊጋርጡበት አይገባም። ምድር ሁሉ የአላህ ስለሆነች፣ ሰው የእርሱ ወኪል ነውና።

**"የአላህ ምድር ትሰደዱባት ዘንድ ሰፊ አልነበረችምን? አሉዋቸው"** (4፡97)

**“በአላህም መንገድ የሚሰደድ ሰው በምድር ዉስጥ ብዙ መሰደጃንና ምቾትን ያገኛል። ወደ አላህና ወደ መልክተኛውም ስደተኛ ሆኖ ከቤቱ የሚወጣ፣ ከዚያም (በመንገድ) ሞት የሚያገኘው ሰው ምንዳው በእርግጥ በአላህ ዘንድ ተረጋገጠ። አላህም መሐሪ አዛኝ ነው።”** (4:100)

**“ምድርንም መልካሞቹ ባሮቼ ይወርሷታል ማለትን ከመጽሐፉ (ከተጠበቀው ሰሌዳ) በኋላ፣ በመጽሐፎቹ በእርግጥ ጽፈናል።”** (21:105)

*ይህ የእስልምና ዕይታ ተከታዩን በክልል/ድንበር ወይም የህዝብ ወሰን እንዳያስብ ይጠብቀዋል፡፡*

*አንድ ሰው ለእምነቱ እና መልካም ዕሴቶች ህያውነት ሲል የሚያደርገው ስደት በእስልምና ከፍተኛ ደረጃ አለው፡፡ በርካታ ነቢያት የተሰደዱ ሲሆን የነቢዩ ሙሐመድ* (ሰ.ዐ.ወ) *ስደት የእስልምና ቀን መቁጠሪያም መጀመሪያው ነው፡፡*

*እስልምና ለስደት ባለው አመለካከት በክልላዊነት/ድንበራዊነት ላይ ያለው ክህደት ምሳሌ ሲሆን፣ አንድ ሰው ከመሬቱ እና ክልሉ/ድንበሩ ዕሴቶች ሊበልጡበት እንደሚገባ ያስተምራል፡፡ አንድ ሰው ለመሬቱ ወይም ክልሉ/ድንበሩ ባለው ታማኝነት የተነሳ ዕሴቶችን መጉዳት በእስልምና ታላቅ ጥፋት ነው፡፡*

**"…የአላህ ምድር ትሰደዱባት ዘንድ ሰፊ አልነበረችምን? አሉዋቸው፤ እነዚያም መኖሪያቸው ገሃነም ናት፤ በመመለሻነትም ከፋች!"** (4፡97)

"የአላህ ምድር… ሰፊ አልነበረችምን?" የሚለው ገለጻ ብሔራዊ ድንበር በእስልምና መሰረት እንደሌላቸው አመላካች ነው። ለአምላክ ተብሎ የሚደረግ ስደት፣ ለመልካም ዕሴቶች ሲባል መሬት እና ክልል/ድንበርን መተው በእስልምና ከፍተኛ ደረጃ ያለው ተግባር ነው፡
፡

**"እነዚያ ያመኑትና እነዚያም (ከአገራቸው) የተሰደዱት በአላህም መንገድ ላይ የተጋደሉት እነዚያ የአላህን እዝነት ይከጅላሉ። አላህም እጅግ መሓሪ አዛኝ ነው።"** (2፡218)

**"እነዚያ ያመኑት ከአገራቸዉም የተሰደዱት በገንዘቦቻቸውና በነፍሶቻቸዉም በአላህ መንገድ ላይ የታገሉት አላህ ዘንድ በደረጃ በጣም የላቁ ናቸው፤ እነዚያም እነሱ ፍላጎታቸውን ያገኙ ናቸው።"** (9፡20)

**"በአላህም መንገድ የሚሰደድ ሰው በምድር ዉስጥ ብዙ መሰደጃንና ምቾትን ያገኛል። ወደ አላህና ወደ መልክተኛውም ስደተኛ ሆኖ ከቤቱ**

**የሚወጣ፣ ከዚያም (በመንገድ) ሞት የሚያገኘው ሰው ምንዳው በእርግጥ በአላህ ዘንድ ተረጋገጠ። አላህም መሐሪ አዛኝ ነው።"** (4:100)

የነቢዩ ተግባር እና ስደት ለዚሁ ጉዳይ አፅዕኖት ይሰጣል፡፡ በእስልምና የእምነት ምህዋር የሚሽከረከረው በመልካም ዕሴቶች ዙሪያ ነው እንጂ በመሬት ዙሪያ አይደለም፡፡ ከመካ ምርኪያ በኋላ ነቢዩ እነርሱን ትተው በመካ መኖር ይጀመሩ ይሆን የሚለው ሃሳብ መዲናውያኑን ስጋት ውስጥ ጥሏቸው ነበር፡፡ ነቢዩም ጠርተዋቸው "ከመሬት ጋ ትስስር የለኝም፡፡ እኔ የአላህ ባሪያ እና መልክተኛው ነኝ፡ ፡ ለእርሱ ስል ወደናንተ ተሰደድኩ፤ ሕይወቴም ሞቴም ከናንተው አጠገብ ነው የሚሆነው" አሏቸው፡፡

ምንም እንኳ ነቢዩ ወደ መዲና እንዲሰደዱ ያደረጋቸው ችግር አሁን ቢፈታም ከመሬት ወይም አገር ጋ ግንኙነት እንደሌላቸው ለማሳየት መካን ትተው ወደ መዲና ተመለሱ፡፡

## ዘረኝነት

አል አሰቢያ A Dictionary of modern Written Arabic ጎሰኝነት፣ ዘረኝነት፣ ብሔርተኝነት እና የስብስብ ተቆርቋሪነት ሲል ይበይነዋል፡፡ ኢብን ኸልዱን አል አሰቢያን አጥቂና ሃያል ጎሳ/ነገድ ከጎረቤት ወይም

በአካባቢ ሲገኝ የጎሳውን ህልውና ለማስጠበቅ የሚደረግ የወንድማማችነት ትስስር ነው ይላሉ፡፡

> “የጎሳው አባል ኢፍትሃዊ በሆነ መንገድ ሲስተናገድና ጥቃት ሲደርስበት ውርደት ይሰማዋል፡፡ በርሱ ላይ ጉዳት ደርሰ አልደረሰ ብሎ ሳያገናዝብ ጣልቃ ይገባል፡፡”

ይህ ስሜት አንድ ሰው ለጎሳው ሰው እንዲሰጥ ያደርገዋል፡፡ በጎሰኝነት ዘመን ውስጥ ይህ መሰጠት የደህንነት ማስጠበቂያ ምንጭ ነበር፡፡ ነቢዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) በዚህ ተጠቃሚ ነበሩ፡፡ እስልምናን ማስተማር በጀመሩበት ወቅት የተለያዩ ጥቃቶች መሰንዘር ሲጀምሩ የጎሳቸው መሪ የሆኑት አቡ ጣሊብ “ምንም እንኳ እስልምናን ባይቀበሉም” ነቢዩን ከጥቃት ከለላ ሆነዋቸዋል፡፡ እንዲሁም በተመሳሳይ መልኩ ሁሉም የቁረይሽ ነገዶች በነቢዩ ላይ ዕቀባ ሲያደርጉ፣ በኑ ሐሺሞች የነቢዩ ወገን ስለሆኑ ከእርሳቸው ጎን ቆመዋል፤ እያንዳንዱ የበኑ ሐሺም አባላት እስልምናን እንዳልተቀበሉ ልብ ይሏል፡፡

በዚህ መልኩ ሲታይ አል-አሰቢያህ ተፈጥሮአዊ የደመ ነፍስ ስሜት ነው፡፡ እስልምናን ከተፈጥሮ ጋ የተሳመረ ሃይማኖት እንደመሆኑ፣ ይህን አንድ ሰው ወገኔ ለሚለው ሰው ያለውን ተቆርቋሪነት በበጎ ይመለከተዋል፡፡ ከዚህ ጋ በተያያዘ የነቢዩ የሚከተለውን ብለዋል “ከናንተ መሃከል ምርጡ ጎሳው/ነገዱ በስህተት ጎዳና ላይ እስካልሆነ ድረስ ጥብቅና የሚቆምለት ነው፡፡” (አቡ ዳውድ 41፡ 5101)

በሌላ በኩል አላህ (ሱ.ወ) በሰዎች መሃከል ያለው የጎሳ/ነገድ፣ የአስተሳሰብ ልዩነቶች የእርሱ ጥበብ ማሳያዎች እንደሆኑ ይናገራል፡፡

> **“እላንተ ሰዎች ሆይ እኛ ከወንድና ከሴት ፈጠርናችሁ፤ እንድትተዋወቁም ጎሳዎችና ነገዶች አደረግናችሁ፤ አላህ ዘንድ በላጫችሁ፣ በጣም አላህን ፈሪያችሁ ነው፤ አላህ ግልጽን ዐዋቂ፣ ውስጥንም ዐዋቂ ነው።”** (49፡13)

በዚሁ አንቀጽ ላይ በጎሳ፣ በዘር፣ የነገድ ወይም በዚህ ላይ የቆመን የበላይነት ሃሳብን ይቃወምና፣ በእርሱ ዘንድ በላጩ “በዓመሉ እና ሥራው ምርጡ” እንደሆነ ከአስረግጦ ያስቀምጣል፡፡

አሰቢያ በመጥፎ ሲገልጽ ብቻ ነው እስልምና የሚቃወመው፡፡ የአሰበያን መጥፎ መገለጫ ነቢዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) እንደሚከተለው አስቀምጠውታል፡፡

> “አንድ ሰው ህዝቡን ከፅድቅ ውጭ በሆነ ዓላማ ተግባር ካገዘ የውሃ ጉድጓድ ውስጥ እንደወደቀና ውስጡ ሬሳው በጭራው ተጎትቶ እንደሚወጣ ግመል ነው፡፡” (አቡ ዳውድ፣ 5098)

በተጨማሪም

“ለብሔሩ/ነገዱ የተጣራ፣ ለብሔሩ/ነገዱ የተዋጋ ወይም ለብሔሩ/ነገዱ የሞተ ከኛ አይደለም፡፡”
ብለዋል (አቡ ዳውድ፡ 5121)

ዘረኝነት የራስን ሆነ የሌላን የዘር፣ የጎሳ፣ የነገድ፣ ሃይማኖታዊ ስብስብ በጥቅሉ የመበየንን ስነ ዘዴ ይከተላል፡፡ ጥቂቶች ለሠሩት ጥፋት ወይም ወንጀል አጠቃላይ ስብስቡን ይኮንናል፤ የስብስቡን መጥፎ መለያዎች በመምዘዝ አጠቃላይ ስብስቡን አክፍቶ ያቀርባል፡፡

እስልምና እንዲህ አይነት ጥቅል ፍረጃ እና ስሁት መደምደሚያዎች አይቀበለም፡፡ በነቢዩ ጊዜ የተወሰኑ ተከታዮቻቸው በክርስትያኖችና አይሁዶች ላይ መጥፎ ሃሳብ ማዳበር ጀመሩ፡፡ ይህ ትክክል እንዳልሆነ እና በሰዎች መሃከል የልዩነት መስፈርቱ የፅድቅ እና ኩነኔ ሥራ እንደሆነ የሚገልጽ አንቀጽ ወረደ፡፡

አላህ (ሱ.ወ) እንዲህ ይላል

**“(የመጽሐፉ ሰዎች ሁሉ) እኩል አይደሉም፤ ከመጽሐፉ ሰዎች ቀጥ ያሉ በሌሊት ሰዓቶች እነርሱ የሚሰግዱ ሆነዉ የአላህን አንቀጾች የሚያነቡ፣ ሕዝቦች አሉ። በአላህና በመጨረሻዉ ቀን ያምናሉ፤ በጽድቅ ነገርም ያዛሉ፣ ከመጥፎ ነገርም ይከለክላሉ፤ በበጎ ሥራዎችም፥ ይጣደፋሉ። እነዚያም ከመልካሞች ናቸዉ፡፡ ከበጎ ሥራ ማንኛውንም ቢሠሩ፣**

አይካዱትም አላህም ጥንቁቆቹን ዐዋቂ ነዉ።”

(3፡113-115)

ከዚሁ ጋ በተያያዘ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) በተወሰኑ ሰዎች ሥራ አጠቃላይ ስብስቡን የሚኮንኑን ክፉኛ ወቅሰዋል፡፡

“በርግጥ ከሐሳውያን ሰዎች መሃከል ታላቁ፣ አጠቃላይ ስብስቡን በማነወር ሌላ ሰውን የሚሰድብ ነው” ብለዋል፡፡ (ኢብን ማጃህ፡ 3761)

“በርግጥ ከሰዎች መሃከል ታላቁ ወንጀለኛ አጠቃላይ ነገዱን የሚያነውር ነው፡፡” (አል አደብ አል ሙፍረል፡870)

ዘረኝነት ለዑመያድ ስርዎ መንግስት ህልውና የሰጠ ዕሳቤ ከመሆኑም በላይ የነቢዩ ሙሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) የልጅ ልጅ ሁሴይንን ከነቤተሰቡ የበላ አስተሳሰብ ነው፡፡ የዘረኝነት ጥፋት በዚህም ብቻ ሳያበቃ በታሪክ የሐራህ ዕልቂት- አጠቃላይ የመዲና ህዝብ በዑመያዶች ጦር ያለቀበት ክስተት- ተብሎ የሚጠራውን ነውረኛ ተግባር እንዲከሰት አስችሏል፡፡

አባሳውያን ዑመያዶችን ገልብጠው ስልጣን ለመያዝ የዘረኝነትንን አስተሳሰብ ተጠቅመዋል፡፡ የራሳቸውን ወገኖች ሃይል ለማሰባሰብ ብቻ ሳይሆን በዑመያዶች የዘረኛ አስተሳሰብ ጥቃት ሲደርስባቸው የነበሩትን ዐረብ ያልሆኑትን ሙስሊሞች ጭምር ለማነሳሳት

ተጠቅመውበታል። ይህ የእስልምናን ዓለም ለምዕተ ዓመታት በዘልቀ የእርስ በእርስ ጦርነት እንዲዳከም አድርጎታል።

## ምዕራፍ ሰባት፡ ዕውነተኛዎቹ የህዝብ የአንድነት አላባውያን

በገናናው የብሔርተኛ ዕሳቤ ለብሔራዊ አንድነት እና የጋራ ንቃተ ህሊና መንስኤ ይሆናሉ የተባሉት አላባውያን አሁን አስፈላጊነታቸውን አጥተዋል፡፡ በሰው ልጆች መሃከል በሚገኙ የማህበራዊ ስብስቦች መሃከል ምንም አይነት ልዩነት ሊኖር ስለማይገባ፣ ሁሉም ህዝቦች ተደባልቀው አንድ ህዝብ ይሁኑ ማለት ነው?

የሰው ልጆች ታሪክ እና በማህበራዊ ግጭቶች እና ችግሮች ላይ ያሉት መረጃዎች እንደሚያሳዩት፣ የሰው ልጆች የተለያዩ መስመሮችን እየተከተሉ በበርካታ ስብስቦች እና መደቦች ሲከፋፈሉ በመኖራቸው መደባለቁ ህልው ሊሆን አይችልም፡፡ በአሁኑ ዘመን የምናስተውላቸው ፓለቲካዊ እና ባህላዊ ለውጦች እርስ በእርስ በመግባባትና በአንድነት ረገድ የሰሜኑን ዓለም ከደቡቡ ይበልጥ እየነጠለው ነው፡፡

ከበርካታ የመቻቻል፣ አብሮ የመኖር፣ የሰላም፣ የአንድነት ወሬዎች በተቃራኒ መሬት ላይ ያሉት መራራ እውነቶች እና የለውጦች ፍጥነት፣ እነዚህን ምርጥ ሃሳቦች መሬት ላይ የመውረዳቸው ነገር እያራቁት ይገኛሉ፡፡

በዚህች ዓለም ውስጥ ተኩላዎች እና በጎች እስካሉ ድረስ በመሃከላቸው አንድነት የመፈጠሩ ዕውነታ ሲበዛ ሩቅ ነው፡፡ አንድ

ስብስብ ፓለቲካዊ ቅርጽ ሲይዝ፣ መሰረቱ ምንም ይሁን ከየትም፣ የሌሎች ስብስቦችን አሳማዊ እና ውሻዊ ፍላጎት ስለሚቀሰቅስ ለጥቃትና ለመበላት ይጋለጣል፡፡ በመሆኑም ስብስቡ ክልሉን፣ ፓለቲካዊ እና ኢኮኖሚያዊ ጥቅሞቹን ለመጠበቅ፣ ባህሉንና ርዕዮተ ዓለሙን ጠላቶች ከሚላቸው አካላት የመከላከል ግዴታ ወድቆብኛል ይላል፡፡

በመላው ዓለም በሚኖሩ ህዝቦች መሃከል ስላለው ልዩነት የማቅረብ ፍላጎት የለንም፡፡ ዓላማችን በህዝቦች ስብስብ መሃከል ብሔራዊ ንቃተ ህሊና ስለሚፈጥሩ እና የስሜት ትስስርን እውን ስለሚያደርጉ አላባውያን መፈለግ ነው፡፡

ለብሔራዊ ውህደት አስፈላጊ ናቸው ተብለው በተደጋጋሚ የሚነሱት አላባውያን- ቋንቋ፣ ባህል፣ ታሪካዊ ዳራ እና ዘር- ሚናቸው ያን ያህል እንዳልሆነ እና የአንድን አገር ህዝብ አዋህደው ለመጠበቅ ያላቸው አስፈላጊነት ኢምንት እንደሆነ አይተናል፡፡ በዚህ ምክንያት መሰረታዊ ሳይሆኑ ድንገቴ (Accidental) ናቸው፡፡

በውጭ ወራሪ ጠላት ላይ ለነጻነት እና ክብራቸው የዘመቱ ህዝቦች ዓላማቸውን ካሳኩ በኋላ መሪና ተመሪ፣ የሞላላቸውና የተጨቆኑ/የተገፉ፣ እንደጠበቅነው ፍላጎታችንና የይገባናል ጥቅሞቻችን እና ግቦቻችን ተሟልቷል አልተሟላም ብለው ተለያይተው ሲጋደሉ ታይቷል፡፡ በመሆኑም የወራሪን ሃይል ለመመከት የተደረገው ትግል ወደ ውስጣዊ የመደብ ወይም ብሔር ትግል ይለወጣል፤ ተለውጧል፡፡

ተመሳሳይ ባህል፣ ቋንቋ እና ዘር ያላቸው ህዝቦች ተከፋፍለው አንዳቸው በሌላቸው ላይ ጦር ተማዝዋል፤ እየተማዘዙም ይገኛሉ። ቀደም ብለው የጋራ ንቃተ ህሊና ያዳበሩ ህዝቦች ማህበራዊ ግንኙነቶች ሲለወጡ የአንድነት መንፈሳቸውን አጥተዋል። አሁንም በአዕምሯችን የሚጉላላው ጥያቄ አልተመለሰም፡ *ለብሔራዊ አንድነት ወይም ህዝብ መፈጠር እውነተኛ መሰረቱና ምንጩ ምንድን ነው? የሰዎችን ልብና አዕምሮ ድብን አድርጎ የሚያስተሳስር፣ በውጤቱም የጋራ ጉጉት እና ምጡቅ ሃሳብ መንስኤ ሊሆን የሚችለው ገመድ ምንድን ነው?*

የአልጄሪያ ህዝቦች በፈረንሳይ ቅኝ ግዛት ላይ ሲያምፁ፣ ፍልስጤማውያን ለሰብአዊ ክብሮቻቸው እና ህጋዊ መብቶቻቸው ትግል ሲያደርጉ፣ በቬትናሞችም የነፃነት ተጋድሎ ውስጥ ለህዝብነት አስፈላጊ ናቸው ተብለው የሚጠቁሱት አላባውያን- የጋራ ቋንቋ፣ የታሪክ ውርስ እና የክልልና ኢኮኖሚያዊ ጥቅሞች በህዝቦች መሃከል መቀራረብ እና መግባባት ለመፍጠት አስፈላጊ ሚና ተጫውተዋል።

ነገር ግን ለአልጄሪያውያን፣ ፍልስጤማውያን እና ቬትናማውያን ትግል ከአልጄሪያዊው፣ ፍልስጤማዊው እና ቬትናማዊው እኩል የሚቆረቆሩ ህዝቦች በዓለም ዙሪያ ነበሩ። ጠንካራ የአንድነት መንፈስና ጥልቅ መቆርቆር በዓለም ዙሪያ የሚገኙ ህዝቦችን አስተሳስሯቸዋል።

ይህ የአንድነት መንፈስ በአንዳንዶች ላይ ጠንካራ በመሆኑ ሚስቶቻቸውን፣ ልጆቻቸውን፣ አገራቸውንና ቂያቸውን አስለቅቆ

በሺዎች ኪሎ ሜትሮች አቋርጠዋል አብረው እንዲታገሉ አድርጓቸዋል፡፡ የቋንቋው፣ የባህልም ሆነ የታሪክ አንድነት ለሌላቸው ህዝቦች ህይወታቸውን አሰጥቷቸዋል፡፡

የእነዚህን የነጻነት ቅስቃሴዎች ታሪክ ስናይ፣ በ"ባዕድ" ህዝቦች መሃል ተገኝተው የተዋጉና የጀግንነት ተግባር የፈፀሙ በርካታ ግለሰቦች፣ ከነጻነት በኋላም የአዲሱ ነጻ የወጣው ህዝብ የተከበሩ አባል ሆነዋል፡፡

በተቃራኒው ተመሳሳይ ቋንቋ፣ ባህል፣ ወግና ልማድ እና ከባቢ ተጋርተው በአንድነት መንፈስ ያልተሳሰሩ ህዝቦች እናገኛለን፡፡ ስለመጪው ጊዜ ያላቸው ሃሳብና ፍላጎት ተቃራኒ ነው፡፡ አንድነት የሚመስል ነገር ካለ፣ የላይ ላይ እና ሕይወት የለሽ ሲሆን የዕለት ተዕለት ፍላጎቶቻቸው ከመወጣት የሚያልፍ አይደለም፡፡

መንግስታት እና ገዥ ሊሂቃኖች ከህዝባቸው ጀርባ ወይም ህዝቦቻቸው ቢያውቀም ደንታ ቢስ የሆኑባቸው በርካታ ጦርነቶች አድርገዋል፡፡ በታሪካችን በርካታ አብነቶችን መምዘዝ ይቻላል፡፡ በተቃራኒው የአፍሪካ ወይም የህንድ ህዝቦች ለፍልስጤማውያን፣ አልጄራውያን ወይም ቬትናም ህዝቦች ድል የሚፋጅና ጥልቅ ፍላጎቶቻቸውን አሳይተዋል፡፡

በመሆኑም ታሪካዊ፣ ጂኦግራፊያዊ፣ ፓለቲካዊ፣ ዘራዊ እና ቋንቋዊ ልዩነቶች በሰዎች መሃከል የተሳካላቸው ጋሬጣ መሆን እንዳልቻሉ ሁሉ፣ በሰዎች መሃከል ዘለቄታዊ ትስስር ለመፍጠር በቂ አይደሉም ብለን መደምደም እንችላለን፡፡

## *የጋራ ህመም*

እንዴት በዓለም ዙሪያ የተበተኑ ህዝቦች ጠንካራ የስሜት ትስስር እና የጋራ ሃሳብ ሊያዳብሩ ይችላሉ? በበርካታ ሺህ ኪሎ ሜትሮች የተራራቁ ህዝቦችን አስተሳስሮ ከጎረቤቶቻቸው፣ ሌላው ይቅር ከጓዶቻቸው ጋ የሚያቃቅራቸው ነገር ምንድን ነው? በጥያቄ ውስጥ ያለው አላባውያን የጋራ ህመም ተሞክሮ፣ ከጭቆና አልጠገብ ባይ አካላት የሚደርስ የጋራ ስቃይ ብለን ልንገልፀው እንችላለን።

በተለያዩ ህዝቦች ውስጥ የተስተዋለው የብሔርተኝት እንቅስቃሴ በህዝቦች መሃከል ከተንሠራፋው የጋራ ህመም እና የጋራ የባዶነት ስሜት ጋ መሳ ለመሳ የተያያዘ ነው። የጀርመን ብሔርተኝነት የተወለደው በፈረንሳዬች የሚደርሰው አግላይ ተግባርና ጣልቃ ገብነት ህመም በሁሉም ጀርመኖች ውስጥ በመሰማቱ ነው። በኢጣሊያ፣ ሃንጋሪ፣ ህንድ፣ ኢንዶ-ቻይና እና አልጄሪያም ብሔርተኝነት እንደ ቅስቃሴ የተፈጠረበት ወቅት በአብዛኛው ህዝቦቻቸው በህመም እና ባዶነት ስሜት ተቀስፈው በተያዙበት ወቅት ነበር።

ምዕራብያውያን የኢራን ታሪክ ምሁራን በኢራን ብሔርተኝነት ወይም የብሄራዊ አንድነት ስሜት የተጠነሰሰው ከቶባኮ ቅስቃሴ ጅማሮ ጋ የተያያዘ ነበር ይላሉ። ወቅቱ በርካታ ኢራናውያን የቅኝ ግዛት ግርፊያ የሸነቆጣቸው ወቅት ነበር። በመሆኑም በህዝቦች መሃከል የጋራ ንቃተ ህሊና፣ የብሔርተኝት ስሜት ወይም ብሔረተኝነት የሚወለደው በጋራ ህመም ሲቀሰፉና የጋራ ፍላጎት ሲያዳብሩ ነው።

የጋራ ፍላጎት ለጋራ ሃሳብ መወለድ መንገዱን ይጠርጋል፡፡ ለዚህ የጋራ ሃሳብ ዕውን መሆን በቅስቃሴ ውስጥ ያሉ ሰዎች በሙሉ ሁሉንም አይነት ጉዳት እና ዕጦት በጸጋ ለመቀበል ዝግጁ ያደርጋቸዋል፡፡ የጋራ ፍላጎታቸው በኋላም ላይ የጋራ ንቃታቸውን ይበልጥ ያጠነክረውና በስሜት አስተሳስሯቸው፣ በመጨረሻም የህዝባዊ አንድነትን ዕውን ያደርጋል፡፡

## *የአንድነት አላባውያን*

እስካለንበት ዘመን ድረስ ህልው የሆኑ አገራትን ለመፍጠር መሳሪያ የሆነውን የጋራ ህመም ስናይ፣ በሁሉም ህዝቦች ዘንድ በተመሳሳይ መልኩ ተግባር ላይ የዋለ የጋራ አላባ መሆኑን ማየት እንችላለን፡፡ ለምሳሌ ጀርመናዊውን ፈላስፋ ፊችን (Fichte) የጀርመን ብሔርተኛ ስሜት እንዲቀሰቀስ ዘመቻ እንዲያደርግ ያስገደዱት ሁኔታዎች ወይም ጋንዲን እና ጋሪባልዲን ለህንድና ለጣሊያን ነጻነት እንዳታገሉ ያደጋቸውን ሁነቶች ወይም የፍልስጤማውያንን የነጻነት እና ክብር ትግል ቅስቃሴ እና የሌሎችን ትግሎች ስንመረምር፣ አንድ ግለሰብ ሆነ ስብስቦች በአመጽ ሲነሱና ለነፃነት ትግል ሲጀምሩ ሁለት አላባውያን በሁሉም ውስጥ ጎልተው ይታያሉ፡ መጀመሪያ በበዝባዥ እና ጨቋኝ መሪዎች እና ተቋሞቻቸው የሚደርስባቸው ከፍተኛ የህመም ስሜት እና ሁለተኛ ይህን የጭቆና ቀንበር ለመጣል ከፍተኛ ፍላጎት መኖር፡፡

ፊች ጀርመናውያንን ከፈረንሳይ የፓለቲካ እና ባህል ጭቆና ተጽዕኖ ነጻ ለማውጣት ጥልቅ ፍላጎት ነበረው። ጋንዲ ህዝቡን እና አገሩን ከእንግሊዞች የፓለቲካ፣ የባህልና የኢኮኖሚ ጭቆናና ብዝበዛ ነጻ ለማውጣት ታግሏል። አልጄራውያንም ከፈረንሳይ ወራራ። በመሆኑም የዓለማችንን አገራት ለመፍጠር መንገድ በጠረጉ ቅስቃሴዎች ውስጥ የህመም ስሜት በአንድ በኩል እና ኢፍትሃዊነትን አስወግዶ ፍትሃዊ ስርአት የመፍጠር ፈቀድ በሌላ በኩል ደምቀው ይታያሉ።

ለምን ይሆን በተደጋጋሚ ኢፍታሃዊ አያያዝ፣ ጭቆና፣ በደል፣ ብዝበዛ በበዛባቸው እና በቅኝ ግዛት ወቅት አዳዲስ ህዝቦች (አገራት) የሚወለዱት? ምክንያቱም በእንደነዚህ አስቸጋሪ እና አስከፊ በደሎች ፊት ሰው ከነዚህ ቀምበሮ ለመላቀቅ በሚያደርገው ትግል ውስጥ እውነተኛው ተፈጥሮው ይገለጣል። ምጡቅ ሰብአዊ ዕሴቶችን አስፈላጊነት እና ፋይዳዎቻቸውን ይበልጥ የሚገነዘባቸው በእንደዚ አይነት ትግል ውስጥ ነው።

ሰው አምባገነንነትን፣ ወንጀልን፣ ጭቆናን እና ንቅዘትን ሲጋፈጥ፣ በነዚህ ህሱም ነገሮች በሚደርስበት ህመም ሲሰቃይ በውስጡ የተዳፈነው ለፍትህ እና እውነታ ያለው ናፍቆት ይቀሰቀሳል።

የሰውን ዘር አንድ የሚያደርጉና የሚያዋህዱ ዕሴቶች እነዚህ ናቸው። ሰው የፍትህ፣ የእውነት፣ የአምላክን ጠባቂነት አፍቃሪ ነው። ይህ ፍቅር በሁሉም ቦታ እና ጊዜ በተለያዩ ቅርጾች እና ቀለሞች ይገለጣል።

በዚህ መሰረት የበደል ስሜት፤ በመሪዎችና ተመሪዎች መሃከል ያለው ቅጥ ያጣ ልዩነት መገንዘብ አንድን ስብስብ ከሌለው የሚለየው፣ በሰዎች መሃከል እውነተኛ የልዩነት መስመር የሚያሰምረው ይህ ነው ወደሚለው እንዘነበላለን፡፡

ቲበርሙንድ (Timburmund) የተባለ ምሁር እንዲሁ የአሁኑን ዘመን ህዝቦች በሁለት ምድቦች አስቀምጧቸዋል- የተበደሉ እና ሁሉ ነገር ለነርሱ የሆነ ወይም ኋላ ቀር እና በኢንዱስትሪ የበለጸጉ አገራት፡፡ ይህ ምደባ የአሁን ጊዜ እውነታ ነጸብራቅ ቢሆንም ሙሉ እውነት ግን አይደለም፡፡ የሰውን ዘር በተገዥ እና ገዥ ህዝቦች የምንከፍል ከሆነ፣ የተበደሉ ህዝቦች በሙሉ በአንድ ቡድን ውስጥ መቆም ይችሉ እንደሆነ ማየት አለብን፡፡ በዚህ ጉዳይ ላይ ፍራንዝ ፋነን (Frantz Fanon) የሚከተለውን ይላል፡፡

> "በጥቁሮች ስነ ጽሑፍ ውስጥ የሚንፀባረቀው ጥቁር ትምክህተኝነት ኢምክንያታዊ ካልሆነ ስሜታዊ ነው፡፡ ነጩ ሰው በሰብአዊነት ላይ የቆለለው ክብረ ነክ አስተሳሰብና ተግባር ተቃርኖ ነው፡፡ በነጩ ሰው ንቀት ላይ የተነሳ አብዬት፣ በአንዳንድ ሁኔታዎች በጥቁሮች ላይ የተጫነውን ስድብ እና ማነቆ ወዲያ ማሽቀንጠሪያ ምርጡ መንገድ ነው፡፡
>
> የጊኒ እና ኬንያ ምሁራን ከቅኝ ገዥው ሃይል ሁሉን አቀፍ ውርደት እና ንቀት ጋር

ሲፋጠጡ ምላሻቸው ራሳቸውን ማላቅና ማሞገስ ሆነ፤ የአፍካሪን ባህል ያለጥያቄ ህጋዊ (ላዕላይ) ማድረግ የምዕራቡን ባህል ያለቅሬታ ማድነቅን ተካ።

የጥቁሮች ቅስቃሴ ገጣሚዎች የቆየ እና ጊዜው ያለፈበትን ሃይል በወጣቷ አፍሪካ ላይ አዛመቱ፤ ምክንያታዊነትን ከግጥሞቻቸው አናጠቡ። ፍልቅልቋን ተፈጥሮ በእውርና ጨቋኝ አመክኗቸው ለከፉ። በአንድ ወገን ረብሻ፣ ጥላቻ እና ጠርጣራነት ሲቆሙ፤ በሌላ በኩል ንጽህና፣ አንድነት፣ ነጻነት፣ አድናቆት፣ የምድር ማልማት እና ሁሉን ሰጭነት ቆሙ። በዛ ላይ ሃላፊነት የጎደለው ....”

በፋነን የተጠቆመው ሃላፊነት የጎደለው ጉዳይ በአፍሪካ ህብረተሰብ ውስጥ ያቆጠቆጠውን የጋራ ህመምና ፍላጎት ዓላማንና ግብን በመቅረጽ ረገድ እጅግ ደካማ መሆኑን ነው።

በጥቁሮቹ አህጉር በነጩ ሰው ኢፍትሃዊነትና ጭቆና ላይ የተነሳው ፀረ ኢምፔሪያሊስት ቅስቃሴ ዓላማውን ኢፍትሃዊነትን እና ልዩነትን መንቀልና የሰብአዊ መብቶችን በምትኩ መትከል እስካደረገ ድረስ የፅድቅ ስራ ነው። ነገር ግን በቀለኝነትን፣ ዕብሪትን እና አዲስ አይነት ሁሉ-ነገር-ይገባኛልነትን ሲላበስ፣ መገለጫውን ያላገኘ ለአዲስ አይነት ኢፍትሃዊነት መሰረቱን ይጥላል።

ስለዚህ በየጋራ ህመም እና ፍላጎት መግፍኤ ዕውን የሆኑ ቅስቃሴዎች እና ትግሎች በግባቸው ይፈረዳሉ፡፡ በፅድቅ፣ ፍትህ እና እውነት ይገዛሉ ወይስ ግባቸው የበላይነት፣ አዲስ ይገባኛል-ባይነት እና ጥቅሞችን ማጋበስ አድርገዋል? ይህ ከብሔርተኝነት ቅስቃሴዎች መሪዎች ርዕዮተ ዓለም፣ እምነት እና አተያይ የሚመዘዝ ይሆናል፡፡

የምዕራቡ ባህል ከላይ የተጠቀሱትን አላባውያንን ከጋራ ንቃተ ህሊናውና ብሔራዊ ግንዛቤው ፍቆታል፡፡ የምስራቁ ሊሂቃን-ሙስሊሙ ሆነ አፍሪካዊው- ብሔርተኝነቱን በምዕራቡ ዓለም ዓይን ማየት መርጧል፡፡ ምን ማለት ነው፣ ጠላቶቹ በሸጡለት መሳሪያዎች እና ቁሳቁሶች አገሩን መገንባትና ከጥቃት ለመከላከል ይሞክራል፡፡ መሳሪያዎችን ከጠላቶች መግዛት ምን የሚሉት የዋህነት ነው፡፡

መታደል ሆኖ ባየናቸው የብሔርተኝት ቅስቃሴዎች ውስጥ ከጋራ ህመም እና የጋራ ፍላጎት በተጨማሪ፣ ለፍትህ፣ እውነት እና ነጻነት ያለ ጥልቅ ፍቅር እኩል አስፈላጊ ነበሩ፡፡ እነዚህ አላባውያን ለአንድ ቅስቃሴ ትክክለኛነት እና ህጋዊነት አስፈላጊ ቅድመ ሁኔታዎች አቀብለዋል፡፡

የጀርመን ብሔርተኝነት በዘረኝነት እና ተስፋፊነት ስለተለወሰ ወደሌሎች ህዝቦች መዛመት አልቻለም፡፡ መጀመሪያው አካባቢ አይሁዶችን ከአገር የለሽነት እና ዓለም አቀፍ ውርደት ነፃ ለማውጣት ቅስቃሴ የመጀመረው ፅዮናዊነት አሁን ላይ የዕብሪተኝነት፣ ዘረኝነት እና ጨቋኝ ርዕዮተ ዓለም ወርሷል፡፡

ይህ የፅዮናዊነት ቅስቃሴ የአይሁዶችን የጋራ ህመምና ፍላጎት መገለጫ ቢሆንም በአስር ሚሊዮኖች የሚቆጠሩ አይሁዶችን ጥቅም ለማስጠበቅ የፍልስጤማውያንንና የዐረብ ህዝቦችን ለእርድ ስላቀረበ ተቆርቋሪ ብቻ ሳይሆን ያጣው በዓለም ዙሪያ ያሉ የነጻነት ወዳድ ህዝቦችን ጥላቻ አትርፏል፡፡

በመሆኑም የህዝቦችን ብሔራዊ መለያ እና ድንበር በመወሰን ረገድ ህዝቦችን ለመለየት ሁሉንም አላባውያን ማጤን ግድ ይለናል- ህመማቸውን፣ ለበደላቸው ያላቸው ንቃተ ህሊና ደረጃ፣ የጋራ ፍላጎት ሙቀት እና በመጨረሻም መዳረሻ ግባቸውን፡፡

እነዚህ መሰረታዊ እና አስፈላጊ አላባውያን አንዴ የጋራ ስነ ልቦና እና ስሜት ካዳበሩ የብሔርተኝነትን መሰረትና መንፈስ ይጥላሉ፡፡ እነዚህ መሰረት እና መንፈስ ቅርጽና አካል ስለሚፈልጉ የህዝቡን ተፈጥሮአዊና አካላዊ ድንበሮች ማስመር ይጀምራሉ፡፡

## *ምዕራፍ ስምንት፡ እስላማዊው እኛ እና እነርሱ*

ቅዱስ ቁርአን የነቢዩ ሙሴንና የፈርዖንን ታሪክ በተለያዩ ቦታዎች ላይ ያነሳል፡፡ ነቢዩ ሙሴ ከቀደምት ዕድሜያቸው ጀምሮ እስከ ስደታቸው፤ በምትነዳዋ ቁጥቋጦ ከአምላክ ጋ ያደረጉት ግንኙነት፤ ከፈርዖን እና ጠንቋዮቻቸው ጋ ያደረጉት ትንቅንቅ እና እስራኤላውያን ነፃ እንዲለቀቁ የጠየቁት ጥያቄ በሙሉ ተርኳቸዋል፡፡ ትረካው ስለየእስራኤላውያን ከፈርዖን አገዛዝ ነፃ ስለመውጣታው፤ ፈርዖን በባህር ውስጥ ስለመስጠሙ፤ በበርሃ ውስጥ እስራኤላውያን ስላሳለፉት የአመፃና *ኩፍር* ህይወት እና አምላክ በሲና ተራራ ለሙሴ ስለመገለጡ ሁሉ ያወሳል፡፡ በዚህ ሁሉ ውስጥ ከሙሴ አጠገብ ያልጠፋው ወንድሙ ሐሩን (አሮን) አለ፡፡ ታሪኩ እስራኤላውያን ወደ ተስፋይቱ ምድር ከመግባታቸው በፊት በሙሴ ሞት ያበቃል፡፡

አሁን እየተነጋገርንበት ካለው ጭብት አንፃር በዚህ *የዘፀዓት ትርክት* አንዱን ሃሳብ መዘን እንወያይበታለን፡፡ *የአላህ እና የነቢዩ ሙሳ ያላሰለሰ ወገንተኝት እርሱንና መልእክኛውን በንቃት ለሚነቅፉት ካፊር ሌሎች፡፡* የምንነጋገርበት ሃሳብ የእስራኤላውያን ከነፃነት በፊትና በኋላ ባሳዩት እና በተገበሩት ኩፍር ውስጥ ከተገፉትና እየተሰቃዩ ካሉት ጋ ስለሚኖር የእኛነት (ወገንተኝነት) ጥያቄ ይሆናል፡፡ የሚከተሉት የቅዱስ ቁርአን አንቀፆች ከሃሳባችን ጋ በቀጥታ ቁርኝት አላቸው፡፡

**“ለሙሳም ከፈርዖንና ከሹማምንቶቻቸው ማሰቃየትን ከመፍራት ጋር ከወገኖቹ የኾኑ *ዙርሪያ* እንጂ አላመኑለትም። ፈርዖንም በምድር ላይ በእርግጥ የኮራ ነበር። እርሱም በእርግጥ ወሰን ካለፉት ነበር። ሙሳም አለ፡- «ሕዝቦቼ ሆይ! በአላህ አምናችሁ እንደ ሆነ በርሱ ላይ ተጠጉ። ታዛዦች እንደ ሆናችሁ (በአላህ ላይ ትመካላችሁ)።» አሉም፡- «በአላህ ላይ ተጠጋን። ጌታችን ሆይ! ለበደለኞች ሕዝቦች መፈተኛ አታድርገን።»”** (10፡83-85)

**“የእስራኤልንም ልጆች ባሕሩን አሳለፍናቸው። ፈርዖንና ሰራዊቱም ወሰን ለማለፍና ለመበደል ተከተሏቸው። መስጠምም ባገኘው ጊዜ፡- «አመንኩ። እነሆ ከዚያ የእስራኤል ልጆች በርሱ ከአመኑበት በስተቀር ሌላ አምላክ የለም። እኔም ከታዛዦቹ ነኝ» አለ።”** (10፡90)

የእስራኤላውያን እምነት ወይም እምነት አለመኖር በቅዱስ ቁርአን የትንታኔ መፅሐፍት ውስጥ በስፋት ያልተዳሰሰ ነገር ነው። ከላይ በተጠቀሰው መልኩ ርዕሰ-ጉዳዩ በተነሳባቸው አንቀፆች ውስጥ ተንታኞቹ አትኩሮታቸው ወደሌላ ተዛማጅ ጉዳይ ይዞራል። በዚህ ጉዳይ ላይ በተንታኞቹ ከሚታየው የአትኩሮት አናሳነት ባሻገር፣ ነፃ ከመውጣታቸው በፊት እጅግ አብዛኛው እስራኤላዊ በአምላክ ላይ ሆነ

በመልእክተኛው ሙሴ ላይ እምነት እንዳልነበራቸው ስምምነት አለ፡፡ ተንታኞቹ እንደሚሉት እነዚህ አንቀፆች የወረዱት እንደ ሙሴ አብዛኛው ህዝባቸው በእርሳቸውና በአምላክ ላይ እምነት በማጣቱ እየተጨነቁ የነበሩትን ነቢዩ ሙሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) ለማፅናናት ነው ሲሉ ይጠቁማሉ፡፡ በነቢዩ ሙሐመድ ላይ ህዝባቸው እንዳመፀባቸው፤ በሙሴም ላይ ህዝባቸው አምፆባቸው ነበር (አል ራዚ፣ 1990፣ 17፣ ገፅ 150፤ አል ነሳፊ ማስታወሻ 3፣ ገፅ 277)፡፡

ቅዱስ ቁርአን በሙሴ ላይ እምነት ያላቸውን *ዙርሪያ* ብሎ ነው የሚገልፃቸው (ቁርአን 10፡83)፡፡ ይህ ደግሞ “በጣም ትንሽ ወይም ከቁጥር የማይገባ” (ኢብን አባስ፣ በአል ራዚ 1990 ገፅ 17፣ 150፣ አል ነሳፊ ማስታወሻ 3፣ ገፅ 277)፤ “ዝርያቸው” (አል ዘመኽሽሪ ማስታወሻ ቁጥር 2፣ ገፅ 364፤ አል ባይዳዊ፣ ማስታወሻ ቁጥር 3፣ ገፅ 277) ወይም “ከወጣቶቹ ጥቂቶቹ” (ሪዳ 1980፣ 11፣ ገፅ 469) ተብሎ ተፈቷል፡፡

ነቢዩላህ ሙሳ (ዐ.ሰ) እውነተኛ *ሙስሊሞች* ከሆናችሁ እምነታችሁን በአላህ ላይ ጣሉ ተማጥኖ፣ ተንታኞቹ ህዝቡ በእርግጥ አማኝ ነበር ማለትን ሳይሆን የሚያሲዘው ከተማጥኖ ያላለፈ ሚና የለውም ሲሉ ይከራከራሉ (ሪዳ 1980፣ 11፣ ገፅ 470)፡፡ “በአላህ ላይ ተጠጋን፡፡ ጌታችን ሆይ! ለበደለኞች ህዝቦች መፈተኛ አታድርገን፡፡” (ቁርአን 10፡ 85) እና “በእዝነትህም ከከሐዲ ህዝቦች (ካፊሩን) አድነን፡፡” (ቁርአን 10፡ 86) ፀሎት በነቢዩ ሙሴ የእውነት ያመኑት የዙርሪያቶቹ ነበር፡፡ በቅዱስ ቁርአን 10፡90 ፈርዖን እስራኤላውያን በሚያምኑት አምላክ

እንዳመነ ይናገራል። ኢብን አባስ እንደሚሉት እዚህ ላይ እስራኤላውያን የምር አማኝ የሆኑት የነቢዩ ሙሴ (ዐ.ሰ) ጥቂት ደቀ መዝሙሮች ናቸው (ማስታወሻ 2፣ ገፅ 282)። አል ራዚ በበኩላቸው እስራኤላውያን ለጣዖት አምልኮ የነበራቸውን ከፍተኛ ዝንባሌ አንስተው፣ ፈርዖን በመጨረሻው ቅፅበት በእስራኤላውያን አምላክ አምናለሁ ብሎ ተጨማሪ ክስረት ጨምሮ ሞተ ብለዋል (አል ራዚ፣ 1990፣ 17፣ ገፅ 162)።

ቅዱስ ቁርአን እስራኤላውያን ወደ ተስፋይቱ ምድር ባደረጉት ጉዞ በሙሉ በክህደታቸው እና ልግመኝነታቸው እንደፀኑ ያስታውሳል። የራሳውን ነፃነት ጨምሮ በርካታ ተዓምራቶችን ቢመሰክሩም ከነርሱ ጥቂቶቹ በስተቀር (ቁርአን 26፡67) በነቢዩላህ ሙሳ (ዐ.ሰ) ጥሪ አላመኑም ነበር። በተቃራኒው ጣዖት ጠርበው አምልከዋል (ቁርአን 2፡51፤ 20፡ 85-97)። እንዲሁም ከሙሴ ጋ ሲያወሩ "(ለ)ጌታህ" እያሉ ነበር አምላክን የሚጠሩት- "ጌታህን ከዚያ ምድር ከምታበቅለው ሁሉ ከቅጠላ ቅጠል ከዱባዋም ከስንዴዋም ከምስርዋም ከሽንኩርቷም ለኛ ያወጣል ዘንድ ለምንል" (2፡ 61)። ልቦቻቸው እጅግ ከመጠጠሩ የተነሳ "እንደ ድንጋዮች ወይም በድርቅና ይበልጥ የበረታች ናት" ይላል ቅዱስ ቁርአን (2፡74)። ለነፃነታቸው እንዲታገሉ በነቢዩ ሙሴ ሲጠየቁ "ኺድ አንተና ጌታህ ተጋደሉ፤ እኛ እዚህ ተቀማጮች ነን" ብለው ነበር የመለሱት (5፡24)። "አላህን በግልፅ እስከምናየው ድረስ ላንተ በፍፁም አናምንልህም" (2፡55) ሲሉ ሙሴን አንጓጠዋቸዋል። ይህን ብለው ብዙም ሳቆዩ አምላክ "ከሰጠናችሁ ጣፋጮች ‹ብሉ› (አልን)" ብሏቸዋል (2፡57)። አሁንም አሁንም በአመፃቸው ላይ

ቢገፉበትም “ይህችን ከተማ ግቡ። ከርሷም በሻችሁት ስፍራ ሰፊን (ምግብ) ተመገቡ” ተብለው ተጋብዘዋል (2፡58 7፡161)። ነፃነታቸውን እና መኖራውን በተመለከተ በእምነታቸው ላይ የተንጠለጠለ (ወይም ከእምነታው ጋ የተቆራኘ) ነገር አልነበረም፡ “በናንተም ላይ የአላህ ችሮታና እዝነቱ ባልነበረ ኖሮ በእርግጥም ከጠፊዎቹ በኾናችሁ ነበር” (2፡64)።

## የዘፀአት ትርክት ጭብጡ

አላህና መልእክተኛው ነቢዩ ሙሴ (ዐ.ሰ) ከፈርዖን እና ደጋፊዎቹ ጋር በነበራቸው ግንኙነት ውስጥ፣ በአንድ በኩል እስራኤላውያን በሌላ ደግሞ ነፃነትን በተመለከተ በርካታ አስፈላጊ ጭብጦችን መምዘዝ ይቻላል።

1. እስራኤላውያኑ በኩፍራቸውና ዕብሪታቸው በቋሚነት ቢገፉም የተስፋይቱ ምድር እስኪደርሱ ድረስ አላህም መልእክተኛውም ሙሳም አልተዋቸውም ነበር።
2. በእስራኤላውያን ኩፍርና በፈርዖን ኩፍር መሃከል የተሳካ ልዩነት ተበጅቷል።
3. ነፃነት አላህን ለማምለክ እንደ ቅድመ ሁኔታ ተቀምጧል፣ አላህን ማምለክ የግድ ባይሆንም።
4. በባርነት ወቅት እነርሱን ከመስበክ ይልቅ ከጎናቸው መቆም የነቢዩ ሙሴ ነቢያዊ ሃላፊነት ሆኗል።

5. ሙሳ ለእስራኤላውያን የጭቆና ቁስላቸውን የሚያስታምሙበት ማስታገሻ አልሰጣቸውም፤ ከጎናቸው ቆመ እንጂ፡፡
6. ከእስራኤላውያን ጎን መቆም ማለት ከፊርዖንና ደጋፊዎቹ ተፃራሪ ሆኖ መቆም ማለት ነው፡፡
7. ከተገፉትና ከተጨቆኑት ጎን መቆም፣ ቅዱስ ቁርአን ሙስሪፉን (አባካኞች) ወይም ሙስተክቢሩን (ዕብሪተኞች) ብሎ በሚጠራቸው ላይ መነሳት በሁሉን ደራሽ የአላህ በረከት ወይም በሁሉን አቀፍ የነቢያቱ ተልዕኮ ላይ ማመፅ አይደለም፡፡

## አማኝ ባይሆኑም ከተጨቆኑት ጋ አጋር መሆን

በእስራኤላውያን ጠንካራ እና ቋሚ ኩፍር ውስጥ አላህም ነቢዩ ሙሴም እስራኤላውያኑ ቃል ወደተገባላቸው ምድር እስኪደርሱ አልተዋቸውም ነበር፡፡ "አላህን አናጋሪ" የሆኑት ሙሴ በአምባ ገነኑ ፊርዖን ፊት ሆነ፣ ከዚያም በኋላ ዕለት ከዕለት እገነገነ በመጣው ኩፍራቸው- ኩፍር በክህደት ሆነ አመስጋኝ ባለመሆን መገለጫው- ውስጥ ንቁ አጋራቸው እና ያለተቋረጠ ወገንተኝነታቸውን እንዲሰጡ ሃላፊነት ተሰጧቸዋል፡፡ እነዚህ ኢአመስጋኝ እና ከሃዲ ህዝቦች ሲማቅቁበት በነበረው ጭቆና (2፡49፤ 7፡137) የተነሳ፣ ቅዱስ ቁርአን በበርካታ ቦታዎች በአላህ በልዩ መልኩ እንደታዩ ያነሳል (2፡47፤ 5፡ 20)፡፡ ለዚህ የተጨቆነ ስብስብ፣ ለጣዖት አምልኮ ያላቸው ከፍተኛ

ዝንባሌ ሳይዘነጋ፣ አላህ ፀጋውን ሊያፈስባቸው፣ መሪ ሊያደርጋቸው እና ወራሽ ሊያደርጋቸው ቃል የገባው (28፡5)። አምላክ እስራኤላውያን "ከታላቅ ጭንቀት" አዳናቸው፤ "ረዳቸውም። እነርሱም አሸናፊዎች ነበሩ" (37፡115-116)። በመጨረሻም በ"ምስጉኑ ስፍራ በእርግጥ" አሰፈራቸው (10፡93)። በነዚህ ሁሉ ውስጥ አላህ ለተገፉት፣ ለተጨቆኑት፣ በባርነት ውስጥ ለሚማቅቁት ስላለው ያልተቋረጠ እና አንዱን ከሌላው ያለየ ወገንተኝነት አይነታ ምሳሌ እናገኛለን።

## በፈርዖን ኩፍር እና በእስራኤላውያን ኩፍር መሃከል ያለው ልዩነት

ቅዱስ ቁርአን ስለ ፈርዖን ኩፍር በሚናገርበት ድምፀት እና ስለ እስራኤላውያን ኩፍር በሚናገርበት ድምፀት መሃከል ግልፅ ልዩነት አለ። በመጀመሪያው ላይ ከረር ያለ ሂስ ሲሰጥ ኋለኞቹን ለዘብ ባለ መልኩ ይሃዩሳል። በፈርዖን ጉዳይ ላይ አንድ ሰው ምንም አይነት ሁለተኛ ሃሳብ እንዳይኖረው ቅዱስ ቁርአን፣ ራሱን እንደ አምላክ የማየት እና ከዚህም ጋ በተያያዘ ሌሎችን የመጨቆን ባህሪ ያለው የሚገጥመውን ክፉኛ አሳማሚ ቅጣት እንሚገጥመው ይናገራል (7፡ 130)። ወደ እስራኤላውያን ስንመጣ ግን፣ ቅዱስ ቁርአን ነቢዩላህ ሙሳ (ዐ.ሰ) እስራኤላውያ ከማስፈራራት ወይም ከመርገም ይልቅ ሲያባብሏቸው፣ ሲለምኗቸው ይተርካል (7፡ 138- 141፤ 160-165)።

ቅዱስ ቁርአን 7፡136-7 እንደምሳሌ ሃሳባችንን ያንፀባርቅልናል፡፡ በ7፡ 136 ስለ ፊርዖንና ተከታዮቹ ቅዱስ ቁርአን ይህን ይላል፡ "እነርሱ በተዓምራታችን ስለአስተባበሉም፤ ከእርሷ ዘንጊዎች ስለኾኑም፤ ከእነርሱ ተበቀልን፡፡" ከዚህ አንቀፅ ወዲያው በሚለጥቀው አንቀፅ፣ ፍፁም ተቃራኒ በሆነ መልኩ ሌሎች ከሃዲዎች፣ አስተባባዮች እና ዘንጊዎች ስለሆኑት እስራኤላውያን የሚከተለውን ይላል፡ "እነዚያንም ደካሞች የነበሩትን ህዝቦች ያችን በውስጧ በረከት ያደረግንባትን ምድር ምስራቆቿንም ምዕራቦቿንም አወረስናቸው፡፡ የጌታህም መልካሚቱን ቃል በእስራኤል ልጆች ላይ በመታገሳቸው ተፈፀመች፡፡ ፊርዖንና ሰዎቹም ይሠሩት የነበረውን (ሕንፃ) ዳስ ያደርጉትም የነበረውን አፈረስን" (7፡ 137)፡፡

በሁለቱም አግባቦች ውስጥ ለተበደሉት ከፍተኛ ተቆርቋሪነት ሲኖር፣ በጭቆና ውስጥ ከቀኖና ይልቅ ለነፃነት መንገድ ቅድሚያ ይሰጣል፡፡ እዚህ ላይ ሪዳን ለመጥቀስ "ከፍትህ ይልቅ ትክክለኛ ነገር የለም፤ ከአምባገነንነት የከፋም ክፋት የለም" (1980፣ 4፣ ገፅ 45)፡፡

## ነፃነት እና እምነት

ከረጅም ስደት እና የመጀመሪያው ወህይ ከወረደላቸው በኋላ፣ ነቢዩ ሙሴ (ዐ.ሰ) ወደ ግብፅ ከተመለሱ በኋላ ለፊርዖን የተናገሩት የመጀመሪዎቹ ቃላት እነዚህ ነበሩ፡ "እኛ የዓለማት ጌታ መልእክተኞች ነን፡፡ የእስራኤልን ልጆች ከእኛ ጋር ልቀቅ" (26፡ 16-17፤ 7፡105)፡፡ ቅዱስ ቁርአን ከነቢዩ ሙሴ እና ከፊርዖን ጋ

የተደረገውን ቃለ ምልልስ ሲያነሳ አንድ አንባቢ ራሱን በዚህች ዓለም ግልፅ ፍላጎት እና በመጪው ዓለም አይቀሬ ፍላጎቶችና እምነት መሃከል ሲንሸራሸር ያገኘዋል፡፡ በመሆኑም፣ የፈርዖን አምላክን መካድ ከዕብሪቱ እና ባለስልጣንነቱ ጋ ተቆራኝቷል፡፡ በተመሳሳይ መልኩ በባርነት ጊዜያቸው የእስራኤላውያን ኩፍር ሆን ተብሎ ከተፈፀመ ክህደት ይልቅ አቅም ካለማግኘት ጋ ተያይዟል፡፡

## በጭቆና ውስጥ የነቢያት ሚና

በግብፅ የባርነት ጊዜያት ነቢዩ ሙሴ ከእስራኤላውያን በነበራቸው ቆይታ በአንድ አምላክ የማመን ቀኖና እንደ አስፈላጊ አላባ ተጠቅሶ አያውቅም፡፡ በተቃራኒው፣ በዚህ ጊዜ የነቢዩ ሙሴ ተቀዳሚ ተልዕኮ እስራኤላውያንን መስበክ ሳይሆን ከጎናቸው መሆን ነበር፡፡ ቃል የተገባላቸውን ምድር ከወረሱ በኋላ ነበር አምላክ የሞከራቸው (2፡ 129)፤ ወደ እምነትም ጥሪ የተጀመረው ከዚያ ጊዜ በኋላ ነበር (20፡ 82)፡፡

## ወገንተኝነት ከምፅዋት ሲለይ

ሙሴ ምንም እንኳ መነሻቸው ባሪያ ቢሆንም ያደጉት በፈርዖን ቤተሰብ መሃል እጅግ ቅምጥል በሆነ ህይወት ውስጥ ነበር፡፡ ሆኖም ይህ ሙሴ አልነበረም ህዝባቸውን ነፃ ለማድረግ የተንቀሳቀሰው፡፡ እጅግ ረዘም ላለ ዓመታት በቀን ሠራተኝነት በስደት ከዝቅተኛው

የህብረተሰብ ወለል በታች ሆኖ አሳልፏል (28፡ 22-28)፡፡ የዚህ ማህበረሰብ አካል ሆነው ነበር ከህዝባቸው ጋ ለመሆን ወደ ግብፅ የተመለሱት፡፡ ግብፅ ከደረሱ በኋላ ፈርዖንን የህዝባቸውን የባርነት ይዞታ ለማሻሻል ሳይሆን ነፃ እንዲለቃቸው ነበር የጠየቁት፡፡ ሙሴ ከአባካኞቹና ዕብሪተኞቹ ጋ ሆነው፣ ባላቸው ስልጣን የህዝባቸው ይዞታ ማሻሻል ይችሉና፣ ታሪኩ የተለየ ይሆን ነበር፡፡ ነገር ግን የፈርዖን አጠቃላይ ስርዓት ኢፍትሃዊ እና የነቀዘ በመሆኑ፣ ምፅዋት ከመስጠት ይልቅ የወገንተኝነትን መንገድ መረጡ፡፡

**የነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ተሞክሮ**

ለበርካታ ዓመታት ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) በመካ ኮረብታዎች በእረኝነት ቆይተዋል፡፡ ምንም እንኳ ወጣት እና ከመካ "ከተማ" ህይወት የተነጠሉ ቢሆንም በተለያዩ ምክንያቶች የሚነሳውን የጎሳ ግጭቶች ይሰማሉ ወይም ያያሉ፡፡ በመካ የጎሳ ግጭት የነዋሪው አንድ የህይወት ገፅታ ነበር፡፡ እናም አንዳንድ ብልጣ ብልጦች ይህን ግጭት በመጠቀም ወገን የሌላቸውን እየመዘበሩ ከርሳቸውን ይሞላሉ፡፡ በአንድ እንግዳ የመናዊ ላይ የሆነውም ይህ ነበር፡፡

ዛቢድ ከምትባል የየመን ከተማ አንድ ነጋዴ ወደ መካ ይመጣና ዕቃዎቹን ለዓስ ቢን ዋዕል ይሸጥለታል፡፡ ዓስ ግን በውላቸው መሠረት የሚጠበቅበትን ክፍያ ለነጋዴው አልሰጠውም፡፡ ነጋዴውም

የቁረይሾችን የተከበሩ ሰዎች ብሩን እንዲያሰጡት ወይም ዕቃውን እንዲያስመልሱለት ይጠይቃቸዋል፡፡ ክቡራኑ ከዓስ ጋ ያላቸውን ግንኙነት በማየት ጥያቄውን ሊቀበሉት አልቻሉም፡፡ ሰውየው ግን በቀላሉ እጁን የሚሰጥ አልነበረምና ወደ መካ በመሄድ ወንዶቹንና የፊርህ ጎሳዎች ከእርሱ ጎን እንዲቆሙ ይጠይቃቸዋል፡፡

ይህ የሆነው የፊጃር ጦርነት ከተካሄደ ከአራት ወራት በኋላ ነበር፤ የነጋዴውን ተማፅኖ ተከትሎ፣ ከተይም ነገድ አባል የሆነ አብደላህ ቢን ጀዳን የሚባል መልካም ሰው፤ ከንግድ፣ ከፖለቲካ እና የነገድ ወይም የጎሳ የጥቅም ግንኙነት ተሻግረው፣ በመካ ቅጥ ባጣ ሁኔታ የተንሰራፋውን ኢፍትሃዊነት ለመዋጋትና የደካሞች ወገን ለመሆን በመካ የሚገኙ የነገድ መሪዎችን በሙሉ ወደቤቱ ጋበዛቸው፡፡ ጥሪ ከተደረገላቸው አብዛኞዎቹ በጎ ምላሻቸውን ሰጥተው ከቤቱ ተገኙተው፤ ግጭት ሲነሳ ሊገላግሉ፣ የጨቋኙን ሆነ የተጨቋኙን ነገድ ወይም ጎሳ ሳያዩ ከተጨቋኙ ጎን ሊቆሙ ቃል ተጋቡ፡፡ ይህ ስብስብ በታሪክ ውስጥ *ሂልፈል ፉዱል*፣ የፃድቃኖች ሊግ እየተባለ ይጠራል፡፡

ለሂልፈል ፉዱል ህልውና የቅርብ ምክንያቱ በየመን ነጋዴው ላይ የደረሰው በደል ነበር፡፡ እናም ይህ ሊግ (ስብስብ) መጀመሪያ የወሰደው እርምጃ በዚህ የመናዊ ነጋዴ ላይ የደረሰውን በደል መቀልበስ ነበር፡፡ እናም ነጋዴውን ወደ በደለው ወደራሳቸው ወገን ወደሆነው ዓስ ቢን ዋዕል ሄደው የነጋዴውን ንብረት እንዲመልስ አደረጉት፡፡ ይህ ስብስብ ከእስልምናም በፊት ሆነ በኋላ ታዋቂ የነበረ ስብስብ ነበር፡፡

ወህይ መውረድ ከጀመረ ከበርካታ ዓመታት በኋላ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ስለዚህ ስብስብ አስታወሱ፡፡ *“ስብስቡ በአብደላ ኢብን ጁዳን ቤት ቃል ሲጋባ ከመሃከላቸው ነበርኩ፡፡ በመሃከላቸው መገኘቴ እጅግ ልቅ ከመሆኑ የተነሳ በሰላሳ ቀያይ ግመሎች እንኳ አልለውጠውም፡፡ አሁን፤ በእስልምና ውስጥ እንኳ የስብስቡ አባል እንድሆን ብጠየቅ በደስታ እቀበለዋለሁ”* ብለው ነበር፡፡

ረሱሉ (ሶ.ዐ.ወ) ስብስቡ የቆመለት ሃሳብ በወቅቱ ከነበረው ውዳቂ የጎሳ ወገንተኝነት እንደሚልቅ አፅዕኖት ብቻ አይደለም የሰጡት፤ በተጨማሪም የእስልምናን መልእክት ተሸካሚና አድራሽ ሆነው- ነቢይ ሆነው- ይዘቱን ተቀብለው አሁንም እንደሚሳተፉ አስረግጠው ተናግረዋል፡፡

ይህ ንግግራቸው ለሰዎች ታላቅ ትርጉም አለው፤ ቢያንስ ሶስት ዋና የሕይወት መርህዎችን መውሰድ ይቻላል፡-

ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ስብስቡ የተመሠረተው ወህይ መውረድ ከመጀመሩ በፊት እንደሆነ ተናግረዋል፡፡ የስብስቡ ዓላማ በምንዱባኖች እና ሃይል በሌላቸው ላይ የሚደርሰውን በደል መቃወምና ፍትህን ማስፈን ግድ ነበር፡፡ ይህ ማለት ከእስልምና በፊት ሰዎች በመልካምነትና በቀናነት አርቅቀው ያጸደቁትን መርህዎች እስልምና በመልእክቱ አፅንቶታል፡፡ በዚህ ንግግራቸው ነቢዩ በግልፅ ከሰውነት የመነጨትን የጃሂሊያ ዘመን የፍትህ መርህዎች እና ለተጨቆኑት መቆምን ትክክለኛነት አረጋግጠዋል፡፡

ሁለተኛው አስፈላጊ መርህ፤ በወህይ ዝግመታዊ አወራረድና በነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ተሞክሮ የእስልምና መልእክት ዋልታና ማገር እየተሠራ በነበረበት ወቅት ሙስሊም ባልሆኑ ግለሰቦች ህያው የሆነውን ፍትህን የመፈለግና ለህብረተሰብ የጋራ ዕሴት የመቆምን መርህ ትክክለኝነት ዕውቅና የሰጡት፡፡ የነቢዩ ንግግር በእስልምና ታሪክ ውስጥ እዚህም እዚያም የገነነውን፣ በእስልምና ቃል ኪዳን ተቀባይነት እንዲኖረው እስላማዊ ተፈጥሮ ሊኖረው እና/ወይም በሙስሊሞች መሃከል መደረግ አለበት የሚለውን አስተሳሰብ በግልፅ ክዷል፡፡ አሁንም በድጋሚ አፅዕኖት ለመስጠት፣ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ለፍትህ መቆምንና ለጭቁኖች መወገን ከእስልምና መጣ ከሌላ ትክክል እንደሆነና ለእርሱም ተገዥ መሆን እንደሚያስፈልግ ዕውቅና መስጠታቸው ቁልፍ ነጥብ ነው፡፡

ከላይ ከተጠቀሰው ሀሳብ በመነሳት ሶስተኛውን ስንመዝ፡ የእስልምና መልእክት ከሌሎች የእሴት ስርአቶች የተለየ ወይም የሚጋጭ ዝግ የዕሴት ስርዓት አይደለም፡፡

ገና ከጅምሩ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) የመልእክታቸው ይዘት በእርሳቸው ጊዜ ሲኖሩ ከነበሩት ዐረቦችና ሌሎች ማህበረሰቦች ሲያበረክቱት ከነበረው ነገር ፍፁም ልዩ ነው ብለው አያምኑም ነበር፡፡ እስልምና ዝግ የሆነ ዓለም አልፈጠረም፡፡ ከሌሎች የእምነትና ሃይማኖታዊ ትውፊቶች፣ የመካ ጣዖት አምላኪያን ማህበረሰብ ሳይቀር፣ መሠረታውያንና ዕሴቶች ጋ ሊዛመድ የሚችል ሁሉን አቀፍ የመርህ ስብስቦች ላይ የተመሠረተ ነው፡፡

እስልምና ጭቆናን መከላከል፣ የተጨቆኑትንና የምንዱባኖችን ክብር መጠበቅን ግድ የሚል የፍትህ መልእክት ነው፤ ይህን መልእክት ህያው የሚያደርግ ህጎች ወይም ስምምነቶች ሙስሊሞች ካገኙ፣ የህጎቹ አውጭ ወይም የስምምነቶቹ ባለቤት ሙስሊሞች ሆኑ አልሆኑ መቀበልና ማክበር አለባቸው፡፡ በሃይማኖቱ ዙሪያ ብቻ የሚሽከረከር ቀበሌያዊ ሆነ ክልላዊ ስብስብ ከመገንባት በራቀ መልኩ፣ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) አማኞች በስመ ሁሉን አቀፍ መርህዎች በራሳቸው ዙሪያ ከሚያደርጉት ግርድፍ ዝግ ትብብሮች ስነልቦናቸው እንዲሻገር አሳይተዋል፡፡ ነቢዩ ይዘውት የመጡት የመጨረሻ መልእክት በፍትህ፣ ርትዕ እና የሰዎች ክብር በመጠበቅ ረገድ በመሠረቱ የተለየ ነገር ይዞ አልመጣም፤ ሰዎች በውስጣቸው ያለውን እንዲያስታውሱና እንዲያፀኑ ብቻ ነው የተጣራው፡፡

ስነ ምግባርንም በተመለከተ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ሰዎች በእስልምና ውስጥም ሆኑ ከእስልምና ውጭ እኩልነታቸውን የሚያሳይ ተመሳሳይ ሀሳብ አንጸባርቀዋል፡፡ *"ከእስልምና በፊት ከናንተ ውስጥ የተሻለው (በሰዋዊና ስነ ምግባራዊ መለያዎች)፣ በእስልምና ውስጥም የተሻለ ነው (ሃይማኖቱን ከተረዳው)፡፡"* ብለዋል፡፡ የሰዎች ስነ ምግባር ዕሴቶች ከአንድም ወይም ከሌላ የአስተሳሰብ ስርዓት የተሻገረ ነው፡፡ በእስልምና ውስጥ ሃይማኖቱ የሚያፀድቀውን (በፍትህ መርህ) በቅጡ ለመረዳት እና ምን እንዲለወጡ/እንዲሻሻሉ (ከጣዖት አምልኮ ጋ በተያያዘ) እንደሚፈልግ በቅጡ ለመረዳት ተጨማሪ ዕውቀት መጠየቁ የሚጠበቅ ነው፡፡

**ዊላያህ**[2]

የሚከተለው የቅዱስ ቁርአን አንቀፅ አማኞች ሌሎችን እንደ አጋር እንዳይወስዱ ከሚከለክሉ አንቀፆች መሃከል አንዱ ነው፡፡

> **"እላንተ ያመናችሁ ሆይ! ይሁዶችንና ክርስቲያኖችን ረዳቶች አድርጋችሁ አትያዙ፤ ከፊላቸው ለከፊሉ ረዳቶች ናቸው፤ ከናንተም ውስጥ ረዳቶች የሚያደርጋቸው ሰው እርስ ከነርሱ ነው፤ አላህ አመጠኞችን ሕዝቦች አያቀናም።"** (5፡ 51)

ይህ አንቀፅ ሙስሊሞች አይሁዶችንና ክርስትያኖችን እንደ ዊላያህ እንዳወስዱ ሲከለክል፣ በሌሎች አንቀፆች ክልከላው ካፊሮችንም አካቷል (3፡28፤ 4፡139፤ 4፡144)፡፡ "እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከእናንተ ሌላ" (3፡118)፤ መናፍቃን (4፡89)፤ "ሃይማኖታችሁን ማላገጫ እና መጫወቻ አድረገው የያዙትን" (5፡57)፤ "ጠላቶቼንና ጠላቶቻችሁን" (60፡1)፤ "ከእነዚያ በሃይማኖት ከተጋደሏችሁ፣ ከቤታችሁም ካወጧችሁ፤ እናንተንም በማውጣት ላይ ከረዱ (ከሐዲዎች)" (60፡9)፤ "አላህ በእነርሱ ላይ የተቆጣባቸውን ህዝቦች" (60፡13)፤ "አባቶቻችሁና ወንድሞቻችሁ ክህደትን ከእምነት

[2] ወዳጅነት ዝምድና ወይም ኅብረት

አብልጠው ቢወዱ" (9፡23-4)፤ ጋር አማኞች እንዳይወዳጁ ተከልክለዋል። ከዚህ ክልከላ ጋር በተያያዘ አማኞች የአምላክን ወዳጅነት ብቻ፣ የአምላክን እና የአማኞችን (ሙዕሚኑን) ወዳጅነት (5፡56)፤ የአማኞችን እና የተሰደዱትን (8፡72-3) ወይም የእምነት ባለቤቶት የሆኑትን ወንዶችና ሴቶችን ወዳጅነት (9፡ 70) እንዲይዙ ታዘዋል።

በቅዱስ ቁርአን 5፡55 ለወዳጅነት ብቁ የሆኑ አማኞች ተበይነዋል፡ (እነርሱ) እነዚያ ሶላትን በደንቡ የሚሰግዱ እነርሱም የሚያጎነብሱ ኾነው፣ ምፅዋትን የሚሰጡ። ይህ ደግሞ ጠቅላላ ሙስሊሙን- ሪዳ የዘር ሙስሊሞች እያለ የሚጠራቸው- ከማዕቀፉ ውጭ ያደርገዋል። ከዚሁ ጋ በተያያዘ ሌላ ማየት የሚገባን ነገር በመፅሐፍቱ ባለቤቶች እና በአማኞች መሃከል ቤተሰብ እስከመመስረት የደረሰ ግንኙነት (5፡ 5)፣ ወዳጅነት እንዲመሰርቱ (5፡82) ሲፈቅድ ይታያል። በተጨማሪም ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) እና ተከታዮቻቸው ከሌሎች እምነት ተከታዮች ጋ የጠበቀ ግለሰባዊ ግንኙነቶች መሥርተዋል። እንደዚሁም ሁሉ በነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) መሪነት ቀደምት ሙስሊሞች ከሌሎች እምነት ተከታዮች ጋ ፖለቲካዊ እና በጋራ ጠላትን የመመከት ውል ተዋውለዋል።

እየተነጋገርንበት ያለው ከላይ የተጠቀሰው አንቀፅ፣ ቁርአን 5፡51፣ እንደሌሎቹ ከሌሎች ጋር ዊላያህን እንደሚከለክሉት አንቀፆች በመዲና የወረዱ ናቸው። በመሆኑም በወቅቱ የነበረውን የሃይማኖታዊ-ፖለቲካው ውጥረት የሚያንፀባርቁ ናቸው። የተለያዩ

የቅዱስ ቁርአን ተንታኞች አንቀፁ የወረደበትን ታሪካዊ ዳራ ተርከዋል፡፡

1. በበኑ ቃይኑቃ እና በሙስሊሞች መሃከል ግጭት ሊቀሰቀስ ዳር ሲደርስ፣ የመናፍቆች መሪ ተብሎ በሠፊው የሚታወቀው አብደላ ኢብን ዑቤይ ለበኑ ቃይኑቃዎች ወገንተኝነቱን ያሳያል፡፡ ወደ ነቢዩም (ሰ.ዐ.ወ) ቀርቦም "እኔ የጊዜን ውጣ ውረድ የምፈራ ሰው ነኝና የጠባቂዎዎቼን ዊላያህ የምክድ አይደለሁም" እንዳላቸው ሁሉ ተዘግቧል (አል ጠበሪ 1954፣ 6፣ ገፅ 257፤ አል ዘመክሸሪ ማስታወሻ 1፣ ገፅ 642)፡፡ በሌላ በኩል ዑባዳህ ኢብን ሳሚት እና ከበኑ ዐውፍ ኢብን አል ኸዝረጅ የሆነ ሰው ወደ ነቢዩ ቀርበው ከበኑ ቃይኑቃዎች ጋር የነበራቸውን ተመሳሳይ ግንኙነት እንዳቋረጡና፣ ለነቢዩም "አላህን፣ የእርሱን መልእክተኛ እና አማኞችን ተወዳጅተናል፤ ከኩፋሮቹ እና ወዳጆቻቸው ጭፍሮቻቸው በአላህና በመልእክተኛው እንጠበቃለን" እንዳሉ ተዘግቧል (የቀደመው ማጣቀሻ)፡፡ አንቀፁ የወረደው የኗለኞቹን ተግባር በመደገፍ እና የቀድሞውን ተግባር በመንቀፍ ነው፡፡ "አላህ ኢንብ ዑቤይን ከእነርሱ ጋ ወዳጅነቱን ቢቀጥል እና ግንኙነቱን ባያቋርጥ አላህን እና መልእክተኛውን ሙሉ ለሙሉ እንደተወ እንደሚቆጠር ሊያሳውቀው ነው፡፡" (አል ጠበሪ 1954፣ 6፣ ገፅ 257)፡፡

2. በኑ ቁረይዛዎች ለአቡ ሱፍያን መልእክት ሰደው የቁረይሾችን ጦር ወደነርሱ ክልል እንዲመጣ ሲጋብዙ፣ በእነርሱ እና በአላህ መሃከል የነበራቸውን ስምምነት አፈረሱ፡፡ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) በአቡ ሉባባን ኢብን አብድ አል ሙንዚርን እጅ እንዲሰጡ መልእክት ይልካሉ፡፡ መልእክቱን አድርሶ ከእነርሱ ሲለይ፣ ለእነርሱ በመወገን ስሜት፣ ሊገደሉ እንደሚችሉ በመጠቆም ወደ ጉሮሮው ያመለክታል (ሪዳ 1980፣ 6፣ ገፅ 425፤ አል ጠበሪ 1954፣ 6፣ ገፅ 275)፡፡

3. የተወሰኑ ሙስሊሞች በሶሪያ ካሉ ክርስትያኖች፣ የተወሰኑ ሌሎች ደግሞ በመዲና ካሉ አይሁዶች ጋ የሙሐመድን (ሶ.ዐ.ወ) እንቅስቃሴ እና የጦር ዕቅድ ያከፍሏቸዋል "ከእነርሱ ሃብት ለመጣቀም፣ በብድር እንኳ ቢሆን" (ሪዳ 1980፣ 6፣ ገፅ 425)፡፡

4. አል ጠበሪ (1956፣ 6፣ ገፅ 276) እንደሚሉት በዑሁድ ጦርነት ዋዜማ ወቅት የተወሰኑ ሙስሊሞች ካፊሮቹ በቁጥር በልጠዋቸው ሊያሸንፏቸው እንደሚችሉ ስጋት ይገባቸዋል፡፡ ከነርሱ ውስጥ እምነታቸውን ወደ አይሁድነት ለውጠው የአይሁዶችን ጥበቃ ለመሻት ሲጠይቁ፣ ሌሎች ደግሞ የሶሪያ ክርስትያኖች ለመጠየቅ ያቅዳሉ፡፡

እነዚህ አንቀፁ እንዲወርድ ምክንያት ይሆናሉ ተብለው የተጠቀሱት የተለያዩ ምክንያቶች፣ ሌሎች ዊላያህዎችን ከሌሎች ጋ ከከለከሉ አንቀፆች ጋ ተመሳሳይ መሆናቸው ሊሰመርበት ይገባል፡፡

የቅዱስ ቁርአን ከኩፋሮች ጋ አማኞች ዊላያህ እንዳይገቡ የከለከለው ኢፍትሃዊ እና ህሱም ከሆኑት ጋ እንደሆነ መገንዘብ ይቻላል፡፡ ክልከላው ወደ ተገፉትና ወደ ተጨቆኑት አይሻገርም፡፡ ዊላያህ የከለከሉት የቅዱስ ቁርአን አንቀፆችን ከወደረዱበት ተናዳፊ ሃይማኖታዊ-ፖለቲካዊ ሁነት በተጨማሪ፣ አንቀፆቹን የከበቧቸውን አቃቢ አውዶችና ሌሎች አንቀፆች ማየት ይበልጥ ግልፅ ያደርገዋል፡፡

እየተነጋገርንበት ያለውን አንቀፅ ብናይ እንኳ፣ አውዱ የዕቀባው ማዕከላዊ ዓላማ ቀኖናዊ ሳይሆን፣ በዚህና እና በሌሎች ዊላያህን በከለከሉ የቅዱስ ቁርአን አንቀፆች (3፡22-5፤ 3፡118-120፤ 5፡57፤ 60፡ 8-9)፣ ዕቀባው ለሃይማኖት ብዝሃነት ዕውቅና አስቀድሞ ነው የሚመጣው፡፡

> **“ወደ አንተም መጽሐፉን ከበፊቱ ያለውን መጽሐፍ አረጋጋጭና በርሱ ላይ ተጠባባቂ ሲሆን በውነት አወረድን፤ በመካከላቸውም፣ አላህ ባወረደው ሕግ ፍረድ፤ እውነቱም ከመጣልህ በኋላ ዝንባሌዎቻቸውን አትከተል። ከናንተ ለሁሉም ሕግንና መንገድን አደረግን፤ አላህም በሻ ኖሮ አንድ ሕዝብ ባደረጋችሁ ነበር፤ ግን በሰጣችሁ ሕግጋት ሊሞክራችሁ፣ (ለያያችሁ)፤ በጎ ሥራዎችንም (ለመሥራት) ተሽቀዳደሙ፤ መመለሻችሁ በጠቅላላ ወደ አላህ**

**ነው፤ በርሱም ትለያዩበት የነበራችሁትን ነገር ይነግራችኋል።”** (5፡48)

ከአንቀፁ አውድ ሆነ አንድ ሰው ምናቡ የፈቀደለትን የይሆናል ክስተት ቢያስብ፣ ከሃይማኖታዊ-ሌሎች ጋር ዊላያህ እንዳይገባ የከለከሉት አንቀፆች የወረዱበት አስገዳጅ ቅድመ ሁነቶች ትንኮሳ፣ ጦርነት እና የአማኞቹ ማህበረሰብ ህልውና አደጋ ውስጥ መግባት ነበር፡፡ በአንሳሪ ቃል “እንዲህ አይነቶቹ እያንዳንዱ አንቀፆች ሙስሊም ካልሆኑት ውስጥ በኢስላም ላይ በግልፅ ጦርነት ያነሱ እና በሙስሊሞች ላይ ያላቸው ጥላቻ ከፍተኛ ሆኖ ንቁ ግጭት የመጨረሻው ጫፍ ላይ ከደረሱት ጋ የተያያዙ ናቸው” (1977፣ 2፣ ገፅ 271)፡፡ በዚህ ተጨባጭ ውስጥ ከጠላት ጋ ዊላያህ መግባት ራስን ከመካድ ተለይቶ አይታይም፡፡ አንቀፆቹ በተደጋጋሚ በሚነሷቸው የሙናፊቆችም ተግባራት ውስጥም ማየት ይቻላል (ምሳሌ 3፡26-7፤ 5፡51-60)፡፡

ግልፅ የሆነ የጦርነት ስጋት ሳይኖር በአማኞች ላይ የማያቋርጥ ትንኮሳዎች መኖራቸው ግልፅ ነበር፡፡ በሌሎች አንቀፆቹ ቅዱስ ቁርአን ትንኮሳዎቹና ጥላቻዎቹ እንዴት እንደሚገለፁ ያሳያል፡፡ ቅዱስ ቁርአን አማኞች ሃይማኖታቸው ላይ ከሚያላግጡት ጋ ወዳጅ እንዳይሆኑ ይከለክላል (4፡139፤ 5፡57)፤ እነዚህኞዎቹ እነርሱን ለማንቀዝ ምንም እረፍት የሌላቸው ሲሆኑ፣ በመጥፎ ገጠመኞቻቸው የሚደሰቱ ናቸው፡፡ ***“እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከናንተ ሌላ ምስጢረኛን አትያዙ፤ ማበላሸትን አይገቱላችሁም፤ ጉዳታችሁን ይወዳሉ፥ ጥላቻይቱ***

*ከአፎቻቸዉ በእርግጥ ተገለጸች። ልቦቻቸዉም የሚደብቁት ይበልጥ ትልቅ ነዉ። ልብ የምታደርጉ እንደሆናችሁ ለናንተ ማብራሪያዎችን በእርግጥ ገለጽን።”* (3:118)፤ አማኞች መልካም ነገር ሲያጋጥማቸው ያዝናሉ፤ መጥፎ ነገር ሲገጥማቸው ይደሰታሉ (3:120)፡፡ አማኞች እነርሱ እውነቱን እንደካዱት እንዲክዱ ይመኛሉ (4:89)፤ ከእስልምና በፊት ወደ ነበረው የጎሳ ስርአት እንዲመለሱ ይጓጓሉ (5:50)፡፡ ዊላያህያቸው የተከለከሉት ጠላትነታቸው በግለሰባዊ ማዕቀፍ የታፈነ አይደለም፡፡ ቅዱስ ቁርአን ከመፅሐፍቱ ባለቤቶች እና ካፊሮች ጋ ዊላያህ ከከለከለባቸው ምክንያቶች መሃከል አማኞችን በመጨቆን በመሳተፋቸው ነው፤ በእምነታቸው ምክንያት ከቤታው ያስወጣሉ ጥቃት ያደርሳሉ (60:9)፡፡

## በቅዱስ ቁርአን የዊላያህ ክልከላ ውስጥ እኛ እና እነርሱ

ቅዱስ ቁርአን እንደኛ አገር የተለያዩ የማንነት ልዩነቶች ባሉባቸው አገራት ውስጥ በዚህ ጉዳይ ባለው ዕይታ ላይ ለመወያየት ሁለት ጥያቄዎች መጠየቅ ያለባቸው ይመስለናል፡ 1- ቅዱስ ቁርአን ከሌሎች ጋ ዊላያህ እንዳትገቡ ብሎ ሲያስጠነቅቅ፣ ሌሎችን እንዴት ነው የገለፃቸው? 2- ዊላያህ የሚፈልጉትን አማኞችንስ እንዴት ነው የገለፃቸው?

ቅዱስ ቁርአን አማኞች ዊላያህ እንዳይገቡ የከለከላቸው ስብስቦች የመጀመሪያ መገለጫ “የአማኞችን ሃይማኖት የሚያንቋሽሹ እና በአምላክ ምልክቶች ላይ የሚያላግጡት” ነው፡፡ “የአማኞችን

ሃይማኖት የሚያንቋሽሹ" (5፡57) እና "በአላህ ምልክቶች ላይ የሚያላግጡ" (4፡140) ጋር ዊላያህ እንዳይገባ የሚከለክሉ አንቀፆች ከወረዱበት የተለያዩ ምክንያቶች አንፃር፣ ግልፅ የወጣና ንቁ የሆነ ስድብ እንዲሁም ከሌሎች እምነቶች ጋ ያለመኖር ፍላጎት የተያያዘ መሆኑ ማየት ይቻላል፡፡ ቅዱስ ቁርአን የሌሎች እምነት ተከታዮችን፣ ሙሽሪኮችን (አጋሪዎችን) ጨምሮ እንዴት በስስት መገናኘት እንዳለብን ያለው አቋም ግልፅ ነው (6፡108)፡፡ በ5፡57 አንድ አማኝ የሌላን ሃይማኖት እንዳይሰድብ እንደተከለከለው ሁሉ፣ ያኛውም የአማኞችን ሃይማኖት እንዳይሰድብ ነው፡፡ የእስልምና ሃይማኖት መሠረቱ ህይወትንና ህብረተሰብን መለወጥ እንደመሆኑ፣ ሁለቱም አካላት በስድብ መስጠማቸው ታላቅ ክስረት ነው የሚሆነው፡፡

ሁለተኛ፡ አማኞች እውነቱን እንዲክዱ ከሚታገሏቸው መራቅ እንዳለባቸው ቅዱስ ቁርአን ያስገነዝባል (4፡89)፡፡ "እውነቱ" የቀኖና ወይም የእምነት ሳይሆን ሃይማኖቶቹ ለጭቆና እና ህብረተሰብን ለመከፋፈል ካላቸው ሚና ጋ የተያያዘ ነው፡፡

አማኞች ወዳጅ አድርገው እንዳይዙ የተከለከሉት አማኞችን የሚጨቁኑና የሚያሰቃዩ የሚገድሉ ናቸው (60፡9)፡፡ **"አላህ የሚከለክላችሁ ከእነዚያ በሃይማኖት ከተጋደሏችሁ፣ ከቤቶቻችሁም ካወጧችሁ፣ እናንተንም በማውጣት ላይ ከረዱ (ከሐዲዎች) እንዳትወዳጁ ብቻ ነው፡፡ ወዳጅ የሚያደርጓቸውም ሰዎች እነዚያ እነርሱ ከበዳዮቹ ናቸው፡፡"** ይህ አንቀፅ ከመካ አማኞችን በታቀደና በተደራጀ መልኩ በመጨቆንና እና በማሰቃየት ለማስወጣት

ከተደረገው ሂደት ጋ ተያይዞ የወረደ ነው፡፡ ይህ የሃጢያት ተግባር ከእምነት እጦት ጋ ተያይዞ መነሳቱ እጅግ አስፈላጊ ነገር ነው፤ በግዳጅ ማስወጣት በምንነቱ ፖለቲካዊ ተግባር ነውና፡፡ እዚህ ላይ አምላክ ስለ ህይወት ያለክፍፍል አንድነት እና የአምላክ ሁሉን ተመልካችነት የተሰመረበት ነው፡፡

> **“ወደነዚያም ወደ በደሉት አትጠጉ፤ እሳት ትነካችኋለችና፤ ከአላህም ሌላ ጠባቂዎች የሏችሁም፤ ከዚያም አትረዱም።”** (11፡113)

## የሌሎችን ዊላያህ የሚፈልጉት

ከሌሎች ጋ ዊላያህ የሚከለክሉ የቅዱስ ቁርአን አንቀፆች ዊላያህውንም ስለሚፈልጉ ሰዎች መግፍኤ ያሳያሉ፡፡ በተጨማሪም ለአንቀፆቹ መውረድ ምክንያት ይሆናሉ ተብለው የተዘገቡት ሁነቶች በሙሉ የዊላያህ ፈላጊዎቹን መግፍኤ ይጠቅሳሉ፡ ከአማኞች ማህበረሰብ እና ዕሳቤ ይልቅ ያራስን ፍላጎት ማስቀደም፤ ዒዛ (ሃይል፣ ስልጣን እና ክብር) ፍለጋ፤ የራስን ዘር/ብሔር ፍለጋ/ማስቀደም፡፡

የመጀመሪያውን በተመለከተ የቅዱስ ቁርአን 5፡51 አንስተን በተወያየንበት ክፍል፣ አንቀፁ የወረደበት ታሪካዊ ዳራ ጋ በተያያዘ የራስን ጥቅም ማስቀደም ተነስቷል፡፡ ቀጥሎ ባለው አንቀፅ- 5፡52 የሌሎችን ዊላያህ ስለሚፍለጉ ይህንን ይላል፡ እነዚያም በልቦቻቸው

ውስጥ (የንፍቅና) በሽታ ያለባቸው ሰዎች "የጊዜ መለዋወጥ እንዳያገኘን እንፈራለን የሚሉ" ሲሆኑ፣ በእነርሱ ለመረዳት ሲቻኮሉ ታያቸዋለህ፡፡

ሁለተኛው የሌሎችን ዊላያህ የሚፈልጉ መግፍኤያቸው ሃይል፣ ስልጣንና ክብር ነው፡፡ ከአማኞች ይልቅ የካፊሮችን እርዳታ የሚጠይቁ ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ይጠይቃል፡ እነዚያ ከምእምናን ሌላ ከሐዲዎችን ወዳጆች አድርገው የሚይዙ እነርሱ ዘንድ ልቅናን ይፍልጋሉን? ልቅናውም ሁሉ ለአላህ ብቻ ነው (4፡139)፡፡ በቅዱስ ቁርአን ተንታኞች ዘንድ በአንቀፁ የተጠቀሱት ዊላያህ የተፈለገባቸው ከሐዲዎቹ አንዳንድ አይሁዶች እንደሆኑ ስምምነት አለ፣ ከፍ ብሎ ባለው አንቀፅም- 4፡137- ተጠቁመዋልና (አል ራዚ 1990፣ 11፣ ገፅ 81)፡፡ ቅዱስ ቁርአን የሚነግረን ሙናፊቆቹ በዊላያህ ከካፊሮቹ የሚፈልጉት ሃይል ቅድመ እስልምና በፊት የነበረውን የብሔርተኛ እና ወንዳዊ ስርአት የሚያስጠብቅ ፖለቲካዊ፣ ማህበራዊ እና ኢኮኖሚያዊ ሃይል ነው፡፡ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) እና ተከታዮቻቸው ይህን ስርአት አስጠባቂ በሆነው አመራር ላለመረታት ከፍተኛ ተጋድሎ አድርገዋል፤ ምክንያቱም እስልምና ከቆመበት ነገር ሁሉ ጋ ይጋጫልና፡፡

ሶስተኛው መግፍኤ ጠባብ ብሔርተኝነት የመተው ችግር ነው፡፡ በአዲሱ የመዲና ስርአት ስልጣናቸውንና የህይወት መንገዳቸውን ያጡ የሃይል ባለቤቶች ስልጣናቸውን ለማስጠበቅ እና የነቢዩ ሙሐመድን (ሶ.ዐ.ወ) ስርአት ለማፈራረስ የተጠቀሙበት መንገድ

ነበር፣ ብሔርተኝነት። ይህ ብሔርተኝነት ከእስልምና በፊት የነበረውን የዐረብ ማህበረሰብ ሙሉ ለሙሉ ሊበላ ጫፍ ላይ ደርሶ ነበር። ጎሰኝነት በተውሂድ ሃሳብ ላይ ለተመሠረተው የመዲና ማህበረሰብ ፀር ነበር። በመዲና ከነበሩት አንዳንድ አይሁዶች፣ ሺሽ ኢብን ቄይስ ለምሳሌ፣ ከእስልምና በፊት የነበረውን የብሔርተኝነትን ጠብ ለመቀስቀስ ብዙ ርቀት ሄደዋል (ሊንግ 1993፣ ገፅ 127፤ አል ዘመክሸሪ ማስታወሻ 1፣ 1፣ ገፅ 393)።

አዲሱን የእምነት ማህበረሰብ እና ዕሳቤ የፈጠሩት ብሄሮች ለእንዲህ አንድነታቸውን የሚያፈርስባቸው አስተሳሰብ ይመጣል ብለው ስላልጠበቁ ዝግጁ አልነበሩም። ከአውስ እና ከዝረጅ ነገድ የሆኑ የተወሰኑ ሙስሊም ግለሰቦች፣ በዚህ ብሔርተኝነትን በተከተለ የተንኮል መንገድ ተጠልፈው ለግጭት ጫፍ ደርሰው ነበር። ይህ ሁኔታ ነቢዩ ሙሐመድን (ሶ.ዐ.ወ) ክፉኛ አስቆጥቷል። “እኔ በመሃከላችሁ እያለሁ ወደ ቀድሞ-እስልምና ጎሰኝነት ዘመን ትመለሳላችሁን?” ብለው እንደገሰጿቸው ተዘግቧል። ለዚህ ክስተት ምላሽ ነበር የሚከተለው የቅዱስ ቁርአን አንቀፅ አማኞች ከተወሰኑ የመፅሐፍቱ ባለቤቶች ጋ ዊላያህ እንዳያደርጉ የተከለከሉት።

> **“የመጽሃፉ ባለቤቶች ሆይ! አላህ በምትሠሩት ሁሉ ላይ ዐዋቂ ሲሆን፥ በአላህ ታምራት ለምን ትክዳላችሁ? በላቸዉ። የመጽሐፉ ሰዎች ሆይ! እናንተ መስካሪዎች ሆናችሁ፣ ከአላህ መንገድ መጥመሟን የምትፈልጓት ስትሆኑ፣ ያመነን**

**ሰዉ ለምን ትከለክላላችሁ? አላህም ከምትሰሩት ነገር ሁሉ ዘንጊ አይደለም በላቸዉ። እላንተ ያመናችሁ ሆይ! ከነዚያ መጽሐፉን ከተሰጡት ሰዎች ከፊሉን ብትታዘዙ ከእምነታችሁ በኋላ ከሐዲዎች አድርገዉ ይመልሱዋችኋል። የአላህም አንቀጾች በናንት ላይ የሚነበቡ ሲሆን መልክተኛዉም በዉስጣችሁ ያለ ሲሆን፥ መልክተኛዉም በዉስጣችሁ ያለ ሲሆን፥ አናንተ እንዴት ትክዳላችሁ? በአላህም የሚጠበቅ ሰዉ ወደ ቀጥተኛዉ መንገድ በእርግጥ ተመራ።”** (3፡ 98-101)

*የሺሽ ኢብን ቂይስ አሁናዊ እኩሎቻቸው ርዕዮተ ዓለማቸውን በዘረኝነትና ብሔርተኝነት ላይ የገነቡና ሃይላቸውና ስልጣናቸውን ለማስጠበቅ ይህን እሳት የሚያራግቡ ናቸው። በዘር እና ብሔር ላይ የተመሠረተ ልዩነትን የሚያራግቡ ግለሰቦች/ስብስቦች- ሙስሊም፣ ክርስትያን፣ አይሁድ ሆኑ ሂንዱ- ቅዱስ ቁርአን ያስጠነቀቀንን ካባ የደረቡ ናቸውና ዊላያህ እንዳናደርግ ከልክሎናል።*

